# ጓደኛነት



# እና ሌሎች መሳጭ ታሪኮች

ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ

የካቲት 2010

# የሥነ ምግባር ታሪኮች ስብስብ

## ክፍል - ፩




ትርጉም አባሪ ጽሁፍና ግጥም

**ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ**

ጽሁፍ፣ የሽፋን ምስል፣ ዲዛይንና ግራፊክስ፦ ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ

## አበርክቶ

ጥር 24 1984 ኢ.ም. ይህች ቀን ለውዷ ባለቤቴ ወ/ሮ ሣራ ግርማና ለኔ ልዩ ነበረች። ጅማ ከተማ ላይ የተከናወነው ሰርጋችን ጥር 24 2009 ኢ.ም.የሃያ አምስተኛ ዓመት የትዳር ጉዟችንን የብር ክብረ በዓል ለማክበር በቃን። ማስታወሻነቷም ክፉ ደጉን ከጎኔ ሳትለይ ለተወጣችው፣ ከቃላት አቅም በላይ ውለታዋ ላለብኝ የጥንካሬ ተምሳሌትና የልጅነት ጓደኛየ ይሁንልኝ።

ልጄ ኪሩቤል ብሥራት ከጥልቅ ምክርህ እስከ ጽኑ ድጋፍህ ላደረከው ሁሉ ምስጋና ባይመጥነውም እግዚአብሔር ይባርክህ። እናቴ፣ የኔም ሆነ የባለቤቴ ቤተሰቦችና ጓደኞቼ በእያንዳንዱ ስኬቴ ውስጥ የእናንተ ድጋፍ አለበትና ሁሌም እኮራባችኋለሁ። አብዩ ጴጥሮስ፣ ተሺ፣ ያሬድ፣ ጀማል፣ መታፈርያ፣ ሊቁ፣ አሹ፣ ማሃሙድ፣ ዮናታን፣ ይብለጥ፣ ያየህ ይራድ፣ ዮናስ፣ ፍቅሩና ሌሎችም ልባዊ ምስጋናየ ይድረሳችሁ።

መምህርት አብነት ግርማ፣ መምህር ሙሉጌታ ደሣለኝ እና ጋዜጠኛ እዮብ ካሳ፦ በጽሁፌ ላይ እጅግ ገንቢ የሆነ አስተያየት ከመለገስ ባሻገር ይህች የበኩር ሥራየ እንደ መጽሐፍ ለወግ ትበቃ ዘንድ አቅምና ብርታት ሆናችሁኛልና - እግዚአብሔር ይስጥልኝ።

## *ተዋፅዖ*

በዚህ መጽሐፍ ውስጥ 72 አጫጭር ታሪኮችና 13 ተጓዳኝ ሥነ ግጥሞች ተካትተዋል። እነኝህ ታሪኮች ከተለያዩ መፃህፍት፣ ከተያያዥ መረጃዎች፣ ከማህበራዊና - ሥነምግባራዊ ድረ ገፆች የተሰባሰቡ ቢሆኑም አጠቃላይ የትርጉም ሥራዎቹ፣ አባሪ ጽሁፎቹና ሥነ ግጥሞቹ ግን የኔው ውጤቶች መሆናቸውን በታላቅ ትህትና እገልፃለሁ።

ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ

## አጫጭር ታሪኮች - ማውጫ፡-

# መግቢያ

የዚህች መጽሃፍ ጥቅል አላማ የኛ የምንላቸው ተረቶች፣ ወጎች፣ ብሂሎች፣ ጥቅሶች፣ ፈሊጣዊ አባባሎችና በአጠቃላይ ሥነቃሎቻችን (ፈረንጆቹ - Moral story, Inspirational Story, bedtime story, Motivational booklets, memorable lessons etc . . .) በሚል ከፋፍለው ለታላቅ ሀገራዊ አላማና ግብ የሚጠቀሙባቸውን ማህበራዊ የማስተማርያ ጥበባት አስተዋጽኦ ከማጉላት አንፃር ከተለያየ አቅጣጫ በተሰባሰቡ ታሪኮችና ገጠመኞች የማህበረሰቡ ጉልህ ህፀፅና ቅንዐት ከሆኑት ፀረ ህዝብነት፣ አገር ወዳድነት፣ ሌብነት፣ ታማኝነት፣ ዋልጌነት፣ ጨዋነት፣ ሙሰኝነት፣ ውሸታምነትና መሰል (አሁንም ፈረንጆቹ Antisocial behavior, morality, honesty, dishonesty, lying . . .) ከሚሏቸው ባህሪያት አመጣጠን ጋር አዋዝቶ ማሳወቅ ነው።

ዛሬ ዛሬ የሥነ ምግባር ዝቅተት ጉዳይ ሲነሳ ሁላችንም ጣታችንን የምንቀስረው በወጣትነት እድሜ ክልል ውስጥ በሚገኘው ትውልድ ላይ ነው። በእርግጥ በርካታ የባህሪ ግድፈቶች የሚንፀባረቁት በዚህ ትውልድ ላይ መሆኑ ባያከራክርም የተጠያቂነቱን ድርሻ ለወጣቱ ብቻ ማሸከም ግን - ወደ ጥምር ስህተት የሚመራን ይመስለኛል። አዎ! ለዚህ እውነታ አያሌ ምክንያቶችን መደርደር ቢቻልም በሁሉም ዘንድ ሊታወቅ የሚገባው አንድ መሰረታዊ ሃቅ ግን አለ። ይኸውም ተተኪ ትውልድን በመልካም ሥነምግባር አርቆ የመቅረጽ ዓቢይ ተልእኮ ከወላጆችና ከአሳዳጊዎች ጀምሮ የትምህርት ተቋማትን፣ የመላ ህብረተሰቡንና የመንግስትን ወዘተ . . . ልዩ ጥረትና ክትትል የሚጠይቅ እንደመሆኑ አሁን ለደረስንበት የብልሹ ባህሪይ ድምር ውጤት . . . በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ የእያንዳንዳችን እጅ እንዳለበት በፀጋ መቀበል ይገባናል።

በመሠረቱ ይህ ነባር ችግር ዘመናትን የተሻገረ እንደመሆኑ በአዝጋሚ የጉዞ ሂደት እየተንከባለለ ቀናውን በጠማማ፣ ሥናዩን በእኩይ እየተካና በደካማው ጎናችን ላይ እንዳሻው ተረማምዶ ዛሬ ላይ የደረሰ እንጂ በአንድ ጊዜ ገንፍሎ ድንገት የተከሰተ አይደለም። ታድያ የምንመኘውን <u>"በመልካም ሥነ ምግባር የታነፀ ትውልድ"</u> ማየት ከፈለግን መንስኤውን ከሥሩ መረዳትና ደካማ ጎናችንን አክሞ ማዳን ይጠበቅብናል። ይህም በመሆኑ ለዚህ ሃገራዊ ችግር ቀዳሚው የመፍትሄ እርምጃ <u>"ማስተማርና ማስተማር ብቻ ነው"</u>። ማንን ? ህፃናቱን፣ ታዳጊውን፣ ወጣቱንና፣ ሕብረተሰቡን ሁሉ። እናም አሁን መሬት ላይ ባለው ተጨባጭ ሁኔታ ለምንወቅሰው ትውልድ የሰጠነው ትኩረት እጅግ አናሳ በመሆኑ ሳናስተምር፣ ሳናሳውቅና ተገቢውን ግንዛቤ ሳናስጨብጥ አልፎ ተርፎ አርአያ ሆነን ሳናሳያቸው ባልደከምንበት ማሳ ላይ ያልዘራነውን ለማጨድ እየባከንን የምንገኝ ይመስለኛል።

እንግዲህ እነዚህን ቀስቃሽ ታሪኮች በዚህች መጽሃፌ አማካይነት አሰባስቤ ለመተርጎም ያነሳሳኝም ይኸው ጉዳይ ነው። የበኩሌን አንድ ጠጠር ለመወርወር። ብዙዎች የተሻለ ማድረግ እንደሚችሉ እምነቴ ሲሆን . . . ያደረጉና በማድረግ ላይ ያሉ ልበ ቀናዎችም ታላቅ ምስጋና ሊቸራቸው፣ ሊወደሱና ሊበረታቱ ይገባል። አዎ - አበው ለወጋቸው ነብስ ሲዘሩ "ያለውን የወረወረ . . ." ይላሉና እኔም ለትውልድ ጠቃሚ ናቸው ያልኳቸውን የወግ በረከቶች "እነሆ" ማለት ፈቀድሁ። እናም ይጠቅማሉ፣ ያስተምራሉ ብየ ያመንኩባቸውን ሀሳቦች ለመምረጥ በማደርገው ጥረት ውስጥ አብዛኛዎቹ ታሪኮች እጅግ ከተራራቁ ሃገሮችና የአለም ጥግጋት . . . ከተለያዩ የባህል ጎራዎች . . . ብሎም በአኗኗር ደረጃም ሆነ የጊዜ ልዩነት ከተለያዩ የሕብረተሰብ ክፍሎችና ህዝቦች የፈለቁ እንደመሆናቸው ጥቂት በማይባሉ ታሪኮች ላይ በቀጥታም ይሁን በተዘዋዋሪ ያስተዋልኩት ተመሳስሎ የተረትና ምሳሌዎችን ጥንካሬ፣ አለማቀፋዊ የጋራ ባህሪይና አንድነት እንዳደንቅ አስገድዶኛል።

ከዚህ አንፃር በመጽሃፏ ውስጥ የተሰባሰቡት ታሪኮች ቅድመ አሻራቸውን ሳይለቁና ማህበራዊ ወዛቸውን እንደጠበቁ ሆነው ለልጆች እንዳይሰለቹ፣ ለአዋቂዎች እንዲመቹና በአጠቃላይ ሁሉም አንባቢ በቀላሉ ይረዳቸው ዘንድ እጅግ ከፍተኛ ጥረት የተደረገባቸው ሲሆን ታሪኮቹን ይበልጥ የሚገልጹ ማብራሪያ ጽሁፎች፣ የሚያጎሉ ፈጠራዎችና ለየት ባለ ሥልት መልዕክቶቹን አይረሴ የሚያደርጉ የሥንኝ ቋጠሮዎችን ተጠቅሜያለሁ።

እንግዲህ ከመነሻው ለመግለጽ እንደተሞከረው የዚህ ጽሁፍ አብይ አላማ ከልዩ ልዩ የዓለም ጠርዞችና ማሕበረሰቦች የፈለቁ ታሪኮችና በጎ የህይወት ገጠመኞችን ነቅሰን በማውጣት ትውልድን ማስተማር እንደመሆኑ ከዳግም ህትመት በስተቀር ያለምንም ክልከላ በየትኛውም የሚድያ ዘርፍ ከፊልም ሆነ ወጥ በሆነ መንገድ በተፃፈበት የአማርኛ ቋንቋ ማንኛውም ሰው ምንጩን በመጥቀስ ብቻ መጠቀም እንደሚችል ስገልጽ በደስታ ነው።

*"There's always room for a story that can transport people to another place."*
—J.K. Rowling

ከልብ አመሰግናለሁ
ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ

## "ፍቅር ምንድን ነው?"

እለቱ እጅግ ሥራ የበዛበት ነበር። በግምት ከጠዋቱ ሁለት ሰአት ከሰላሳ ሲሆን በሰማንያዎቹ የእድሜ ክልል ውስጥ የሚገኙ አዛውንት ቀደም ሲል የአውራ ጣታቸው ቁስል የተሰፋበትን ክር ለማስወጣት ሆስፒታል ደርሱ። እንደገቡ ሦስት ሰዓት ላይ የሚሄዱበት እንዳላቸውና በጣም እንደሚቸኩሉ ነገሩኝ። ሃኪሙ የጀመረውን ህመምተኛ እስኪጨርስ አንድ ሰዓት ገደማ እንደሚወስድ አስረዳኋቸውና አረፍ እንዲሉ ወንበር አቀረብኩላቸው።

ሰዓታቸውን ደጋግመው ሲመለከቱ አስተውዬ ሌላ ህመምተኛ ከመጥራቴ በፊት እኔው ልረዳቸው ወሰንኩና ወደሚቀጥለው ክፍል ሄጄ አስፈላጊ ቁሳቁሶችን በማምጣት አውራ ጣታቸውን ለማከም ተዘጋጀሁ። የስፌቱን ክር የመምዘዝና መልሶ የማሸጉን ሥራ እንደ ጀመርኩ ከአዛውንቱ ጋር ጨዋታ ያዝን። እንዲህ የቸኮሉበት ጉዳይ ሌላ ሆስፒታል ከሃኪማቸው ጋር ቀጠሮ ስላላቸው እንደሆን በማለት ጠየኳቸው። አዛውንቱም ሌላ ቀጠሮ ሳይሆን የቸኮሉት በህመምተኞች ማገገሚያ ማእከል ከምትገኝ ባለቤታቸው ጋር ቁርስ መብላት ስላለባቸው እንደሆነ ሲገልጹልኝ እኔም ስለባለቤታቸው ህመምና ስላሉበት ሁኔታ ጠየኳቸው። እሳቸውም ባለቤታቸው በነርቭ መታወክና ከእድሜ ጋር በሚመጣ የመርሳት በሽታ ማገገምያው ውስጥ እንደሚገኙ ገለጹልኝ።

አውራ ጣታቸውን አክሜ ቁስላቸውን አሽጌ ሳበቃ በመዘግየታቸው ምክንያት ይሄኔ ባለቤታቸው ይጨነቁ እንደሆን በማለት ስጠይቃቸው፤ ማን እንደሆኑ እንኳ እንደማያስታውሷቸውና ላለፉት ስምንት አመታት ሲመላለሱም እንዳላወቋቸው ትክዝ ብለው ነገሩኝ። በሁኔታው እጅጉን ተገርሜ - የእርሶን ማንነት እንዳልተገነዘቡ እያወቁ እርስዎ ግን በየእለቱ ጠዋት ጠዋት እየተመላለሱ አብረዋቸው ቁርስ መብላትዎን አለማቋረጦ አስደንቆኛል! ስላቸው፣ ገፃቸው በፈገግታ ተመልቶ እጄን ጨበጦ አደረጉና . . .

"ልጄ . . . በአጠቃላይ ፍቅር እንደዚህ ነው፤ እሷ ባታስታውሰኝም - እኔ አስታውሳታለሁ! እሷ ልታውቀኝ አልቻለችም - እኔ ግን እስካሁን አውቃታለሁ፣ እስከመጨረሻው እረዳታለሁ፣ በየእለቱ ማለዳ ዓይን ዓይኗን እያየሁ ያሳለፍነውን ወርቃማ ጊዜ በህሊናየ እየደገምኩ፣ አጠገቧ ቁጭ ብየ ቁርሴን ስበላ ከምንም በላይ እረካለሁ፣ ለሷ ባለኝ የማያረጅ ጥልቅ ፍቅር በመጽናቴም እጽናናለሁ" አሉኝ።

ለካስ - ፍቅር ፦ እንደዚህ . . . እንዲህና ከዚህም በላይ ነው! ገረመኝ። አዛውንቱን ሰው ተሰናብቼ እስከበሩ ከሸኘኋቸው በኋላ ለደቂቃዎች በቢሮዬ መስኮት የጠራውን ሰማይ እየተመለከትኩ የፍቅርን ጫፍ ከሚታየኝ አድማስ ጋር ማወዳደር ያዝኩ። ፍቅር እየጠለቀ - እየጠለቀ ሰማዩን ዘልቆ አድማሱን ሲሻገር ባይነ ህሊናዬ ታየኝ። ወደ መቀመጫዬ ተመልሼ ወትሮ ሸንቆጥ የሚያደርግ ነገር ሲገጥመኝ እንደማደርገው የግጥም ምሴን ለማድረስ ብእሬን ባዶው ወረቀት ላይ ወደርኩ። በሥራ ምክንያት ሳቋርጥ - ስቀጥል፣ ሳቋርጥ - ስቀጥል በመጨረሻ እንደዚህ ተደረደረ።

### <u>ለካስ ፍቅር ይህ ነው !</u>

አልገባኝም ነበር ? - አላወኩም ነበር ? - ለካስ ፍቅር ይህ ነው
ሳያዩ የሚያምኑት - ሳይቀርቡ - የሚያውቁት - የሚረዱት ቀድመው

ከሸር - ከተንኮል የፀዳ - ሃኬት - ማስመሰል የሌለበት
ከንጹህ መንፈስ ተፈጥሮ - መልካም በረከት ያደገበት

ሸርፈው የማይለግሱት - ገምሰው የማይሸሽጉት
ቆርሰው የማይደብቁት - ቃላት የማይሸምቁት።

በህሊና ድር አብሮ - በልብ ማህፀን የቀና
በጋራ ጥንስስ ጠንክሮ - በሃቅ ማተብ የፀና።

ከአድማስ አድማስ የመጠቀ ፡
ባብሮነት ጽናት የዘለቀ ፡
ጥልቅ ምህላ ወረት አልባ ፡
ምሉእ ወ ብሩክ የተቀባ።

ለሌላ በመሆን መርህ - በህገ መስጠት የከበረ
በእውነት ላይ ተመስርቶ - በግልጽ እስከ ጫፍ የኖረ።

እድሜ ያታና ቀለም - አገር ዘርና ድንበር
ከቶም የማይገድቡት - ካጽናፍ እስካጽናፍ የሚበር
ፍቅር ከዚህም በላይ ነው - የሚኖር - የማይቀየር
የማይጎብጥ የማይሰበር - የማይሞት - የማይቀበር !።
የሚኖር - የማይቀየር - የማይሞት - የማይቀበር . . .።

የፃፍኳትን ግጥም አንዴ አነበብኳትና መሳቢያዬ ውስጥ አስቀመጥኳት። ጠዋት ያገኘኋቸው ሽማግሌ ቀኑን ሙሉ ከምናቤ ሳይጠፉ አብረውኝ ዋሉ ማለት ይቻላል። ረፋድ ላይ ሥራዬን እንደጨረስኩ የፃፍኳትን ግጥም የግል ኮምፒውተሬ ላይ መፃፍ

ከመጀመሬ በፊት የምስል ክምችቶቼን ቃኘት - ቃኘት ሳደርግ ከአንዱ የማህበረሰብ ጉዳዮች ድረ - ገጽ ላይ አግኝቼ ያስቀመጥኩት ምስል ሳበኝ። በፎቶው ላይ ቀን ያጋጠሙኝን አዛውንት - የመሰሉ ሽማግሌ የእኩያ ሚስታቸውን ፀጉር ያበጥራሉ።  ከ ምስሉ ራስጌ - - -

“As We Grow older together, as we continue to change with age, there is one thing that will never change … I will always keep falling in Love with you” የሚል ጽሁፍ ሰፍሯል።

ለምታዩት የእንግሊዝኛ መልእክትና ውስጤን ለነካኝ ምስል በሃገርኛ ቋንቋ እንዲህ ቋጠርኩለት።

እነሆ ከነምስሉ።




ደራሲው፣ ገጠመኙን ያሰፈረውም ሆነ ምስሉ የማን እንደሆን አልተገለፀም።
ምንጭ -  የታሪኩ መነሻ ሃሳብና ምስል  - ከማህበረሰብ ጉዳዮች ድረ ገጽ
ርእስ - "What love is all about"

ጥቅምት  2008 ዓ. ም.  ***  አዲስ አበባ




## "የመጨረሻው ጉዞ"

**የታክሲ ሾፌሩ ማስታወሻ - እውነተኛ ታሪክ ኒው ዮርክ - ዩ. ኤስ. ኤ**

በተሰጠኝ አድራሻ መሰረት ከህንፃው ፊት ለፊት ደርሼ የመኪናዬን ጡሩምባ ተጫንኩ። ጥቂት ደቂቃዎችን ጠብቄ ደገምኩ ። ብቅ ያለ ሰው የለም። ይህ ጉዞዬ ለዛሬ የመጨረሻው ስምሪቴ እንደመሆኑ ዞሬ መመለስ ሲገባኝ እኔ ግን መኪናየን አቁሜ ደረጃውን ሽቅብ በመራመድ በሩን አንኳኳሁ . . . "አንዲት ደቂቃ ብቻ" - ዝግ ብሎ የሚንቀጠቀጥ ድምጽ በበሩ ስር ዘልቆ ተሰማኝ። በትእግስት ብዙ ጠብቄ በሩ ተከፈተና በዘጠናዎቹ የእድሜ ክልል ውስጥ የሚገኙ አጭር ከሲታ አሮጊት ከፊት ለፊቴ ቆሙ። የለበሱት ዥንጉርጉር ቀሚስና ካኪ ፖስታ ከመሰለ ባርኔጣቸው ጋር የተያያዘው አይነርግብ በ 1940 ከተሰሩት ፊልሞች የአንዱ ተዋናይት አስመስሏቸዋል። ጭር ያለው ቤት ለዘመናት ሰው የኖረበት አይመስልም። መሃል ላይ አንድ ትንሽ አሮጌ ሻንጣ ተቀምጧል፣ የቤቱ እቃዎች በስስ ነጭ ጨርቅ ተሸፍነዋል፣ ግድግዳው ላይ ሰአት፣ ጌጣጌጦችም ሆኑ ሌላ ቁሳቁሶች አይታዩም፣ ጥጉን የቆመው የእንጨት መደርደርያ በርካታ ፎቶግራፎችና ብርጪቆዎች ታጭቀውበታል።

በቀስታ. . . "እባክህ - ሻንጣዬን ልትወስድልኝ ትችላለህ?" በማለት ጠየቁኝ።
ፈጠን ብየ ሻንጣውን መኪናው ውስጥ አስገባሁና ደረጃውን ሲወርዱ ለማገዝ ተመለስኩ። ክንዴን ጥብቅ አድርገው እንደያዙ ደረጃውን ወርደን እስከ መንገዱ ጠርዝ በዝግታ ስናመራ በትህትና - "ስለረዳኸኝ አመሰግናለሁ - እግዚአብሄር ይስጥህ !" አሉኝ።

እኔም "አሜን - እማማ ተሳፋሪዎቼን እንደ ወላጆቼ መርዳትና ማገልገል የሞያ ግዴታየ ነው" አልኳቸው።

"በእውነት አንተ ጥሩ ልጅ ነህ - ብሩክ ሁን" በማለት መረቁኝ። መኪናው ውስጥ ገብተን ለጉዞ ስንሰናዳ የሚሄዱበት አድራሻ የተፃፈበትን የተጣጠፈ ወረቀት እያቀበሉኝ "እባክህ በመሃል ከተማው በኩል ልትሄድልኝ ትችላለህ? እንደ ቀለበት መንገዱ አቋራጭና ነፃ እንዳልሆነ ይገባኛል" አሉኝ። "ግድ የለም እወስዶታለሁ" በማለት መኪናዬን አስነስቼ አቅጣጫዬን ከተማውን ሰንጥቆ ወደሚያልፈው ጎዳና በማስተካከል ጉዞ ጀመርን።

የኋላው ወንበር ጫፍ ላይ ኩርምት እንዳሉ ተቀምጠው በተከፈተው መስኮት ውጭውን በስስት ያስተውላሉ፣ ከባርኔጣቸው ስር ሾልከው የወጡትን ስስ ግራጫ ፀጉሮች የምሽቱ ቀዝቃዛ ነፋስ ያወዛውዛቸዋል። እድሜ ዝብርቅርቅ አሻራውን ያተመበት ባለ ብዙ መስመር ፊታቸው፣ ወደ ውስጥ የሰረጎዱት ጉንጮቻቸውና መላ ሁኔታቸው ሃዘኔታን የሚያጭር ድባብ አለው። በከፊል ዘወር ብለው - "ልጄ እኔ ምንም የምቸኩልበት ጉዳይ የለም። የምሄደው ወደ ሆስፒታል ነው" አሉኝ። በኋላ መመልከቻው መስታወት አየኋቸው . . . እንባ ያቋተ አይናቸው ያንፀባርቃል። ንግግራቸውን ቀጠሉ "ምንም የቀረ ዘመድ የለኝም እናት፣ አባት፣ ወንድም፣ እህት፣ ልጅ . . . ሁሉም" ድምፃቸው ተቆራረጠ ስልል ባለ ድምጽ ቀጠሉ "ዶክተሩ ሁሉንም ነገር ነግሮኛል፣ የሚቀረኝ እጅግ ጥቂት ጊዜ ነው። ወደ ምሄድበት ሆስፒታል መግባቴን እንጂ ስለ መውጣቴ የማስብበት ጉዳይ አይደለም። ይህ የመጨረሻው ጉዞየ ነው"። እንዳሉኝ ተንጠራርቼ የታክሲውን የክፍያ ኪሎ ሜትር መቁጠርያ አጠፋሁትና ፍጥነቴን ቀንሼ በዝግታ እያሽከረከርኩ ለስለስ ባለ አንደበት "በየትኛው መንገድ ወደ የትኛው ሰፈር እንድወስዶት ይፈልጋሉ?" በማለት ጠየኳቸው። ከዚያ ወዲያ ያሻቸውን ሥፍራ እየጠቆሙኝ ከሁለት ሰአት በላይ በከተማዋ ልዩ ልዩ መንደሮች ተዘዋወርን።

ወደ አንድ መካከለኛ ሕንፃ እያመለከቱ "ሥራ የጀመርኩት እዚህ ሕንፃ ውስጥ ነበር። ምን እሰራ እንደነበር ትገምታለህ? የህንፃው መወጣጫ አሳንሰር መካኒክ ነበርኩ" አሉኝ። መስቀለኛውን ጎዳና ተሻግረን ወደ ግራ ስንዞር ከባለቤታቸው ጋር በአፍላ የትዳር ዘመናቸው የኖሩበትን ቤት አሳዩኝ። ጉዟችንን ቀጥለን ከአንድ የቤትና የቢሮ እቃዎች መሸጫ ስንደርስ "ጥቂት ዝግ በል – ይህ በጊዜው አለ የተባለ የዳንስ አዳራሽ ነበር፣ በልጃገረድነቴ ሳላሰልስ ደንሼበታለሁ" አሉኝ። እንዲህ እንዲህ እያልን ስንጓዝ አንዳንዴ የተወሰኑ ህንፃዎች ወይም መታጠፊያዎች አጠገብ ቀስ ብዬ እንድቆም ይጠይቁኝና ጥልቁ ጨለማ ውስጥ በዝምታ እንዳፈጠጡ ይቆያሉ። እኩለ ለሊት ተጋምሶ የጎህ ብርሃን በጠራው ሰማይ ላይ ሲፈነጠቅ "አሁን እየደከመኝ መጣ ወደ መዳረሻችን እንሂድ" አሉኝ። ዝም ዝም እንደተባባልን ተጉዘን በሰጡኝ አድራሻ መሰረት ከአንድ አነስ ያለች የአረጋውያን ህክምና መስጫና ማገገምያ ህንፃ ደረስንና ከመግቢያው ትይዩ አቆምኩ። ወዲያውኑ ተሽከርካሪ የህመምተኛ ወንበር የያዙ ሁለት አስታማሚዎች አሮጊቷን ከመኪናው ውስጥ ማውጣት ጀመሩ። ደግነት ከታላቅ ትህትና ጋር የሚነበብባቸው አስታማሚዎች የሚያሳዩት እያንዳንዱ እንክብካቤ እርዳታቸውን ለመለገስ ለሰአታት ሲጠብቋቸው እንደቆዩ ያስታውቅ ነበር።

የመኪናዬን እቃ ማስቀመጫ ከፈትኩና ሻንጣቸውን አውርጄ ተሽከርካሪው ወንበር ላይ ተቀምጠው ወደ ውስጥ ለመግባት ወደሚጠብቁት አሮጊት በመውሰድ ለአንዷ አስታማሚ አስረከብኩ። ምስኪኗ አሮጊት ከጭናቸው ላይ ትንሽዬ የገንዘብ ቦርሳ እያነሱ "ክፍያየ ምን ያህል ይሆናል ?" በማለት ጠየቁኝ።

"ምንም አይከፍሉም" አልኳቸው ፈጥኜ።

"ልጄ - ለመኖር ገንዘብ ያስፈልግሃል" አሉኝ።

"እማማ - ያንን ከሌሎች ተሳፋሪዎች አገኛለሁ" አልኳቸውና በደመነፍስ ወደ ፊት ተራምጄ በስስት አቀፍኳቸው፣ ሆዴ ውስጥ የሆነ ነገር ሲገላበጥ ተሰማኝ፣ ከቦዙት ዓይኖቼ የእንባ ዘለላዎች አፈትልከው ተንጠባጠቡ። በሚንቀጠቀጡ እጆቻቸው ትክሻዬን ጥብቅ አድርገው እንደያዙ "ልጄ - ልጢ ለተራሰ፣ ጉድጓድዋ ለተማሰ፣ ዓለም ለተደፋባት ብቸኛ አሮጊት የመጨረሻ ጉዞዋን ስንቅ በወደር የለሽ ደስታ እስከ መቃብር በሚዘልቅ እንጥፍጣፊ ፀዳል አደመቅከላት። ቃላት የሉኝም - እግዚአብሄር ይስጥህ" አሉ - በሞጨሞጨት አይኖቻቸው ትኩር ብለው እያዩኝ።

ብድግ ብየ እየተደናቀፍኩ ወደ ደብዛዛው የንጋት ብርሃን ተራመድኩ። ከኋላዬ "ጓ" ብሎ በሩ ሲዘጋ ሰማሁ . . . አዎ "ወደ ምሄድበት ሆስፒታል መግባቴን እንጂ ስለ መውጣቴ የማስብበት ጉዳይ አይደለም" የምስኪኗ አሮጊት ቃል ጭንቅላቴ ውስጥ አስተጋባ! ሞትን አውቆ የህይወት ቆይታን በቀናት፣ በሰዓታትና ደቂቃዎች መለካት . . . ምን ይሰማቸው ይሆን? "ይህ የመጨረሻው ጉዞዬ ነው" ያሉኝን አስታወስኩ፣ አጋጣሚው አስገረመኝ። ትክክል ነው፣ ለእርሳቸው በሕይወት ቆይታቸው የመጨረሻው ጉዞ ነበር። ለኔ ደግሞ በእለቱ የመጨረሻው የሥራ ጉዞዬ። ልዩነቱን እያሰላሰልኩ የመንገዱን ቀኝ ጠርዝ ይዤ በቀስታ እነዳለሁ፣ ተሳፋሪ አልጭንም ወዴት እንደምሄድም አላውቅም፣ እንቅልፍ በአይኔ አልዞረም - መተኛት ግን አላሰኘኝም። ደስታ - ሃዘን - እርካታ - ሰቀቀን . . . አእምሮዬ በዝብርቅርቅ ሃሳቦች ተወጥሯል።

ምስኪኗ አሮጊት ታጋሽ ወይም ጥያቄአቸውን ለመፈፀም ፍቃደኛ ያልሆነ ሾፌር አጋጥሟቸው ቢሆን አልያም እኔ ራሴ የመኪናዬን ጡሩምባ እንደወትሮው ደግሜ ሳላሰማ ዞሬ ብመለስ፣ ወይም ደግሞ የመሃል ከተማው መንገድ ርቀቱ አሳስቦኝ እምቢ ብያቸው ቢሆን ኖሮ? ምን ይሆን እንደነበር አሰብኩና ዘገነነኝ። ነገር ግን ይህ እኩይ ቅዠት በቅጽበት በነነና በሌላ ደስ የሚል ሃሳብ ተተካ። መንፈሴ በበጎ ምግባር ሲጽናና፣ እኔነቴ ለላቀ ቅንነት ሲተጋና ሲመሰጥ ይህ ነው የማልለው የሚያነቃቃ ስሜት ውርር አደረገኝ። የፈፀምኩት ተግባር በመላ ህይወቴ ከየትኛውም ዋንኛ ከምላቸው ነገሮች በላይ በሥናይነቱ የከበረ ሆኖ ታየኝ፣ እለቱም ለመጀመሪያ ጊዜ ሰው የሆንኩበት የቃል ኪዳን ማለዳ ሆነልኝ።

ወዳጆቼ - ለሰው ቀና መሆን፣ በጎ ማድረግና መርዳት ከምንም በላይ – እርካታን የሚያጎናጽፍና ከማንም በላይ ታላቅ ሞገስ የሚሆነው ለራስ ነው ለካ። እኔስ ቀናሁ፤ ህይወታቸውን ለዚህ ቅዱስ ምግባር በሰጡ ሰዎች ቀናሁ! ዘወትር በዚህ ቅን ሃሳብ ተጠምደው በሚታትሩ ሰዎች ቀናሁ! ገንዘባቸውን፣ እውቀታቸውንና መሻታቸውን ሁሉ ለዚህ ተግባር በሰጡ ሰዎች ቀናሁ! ምንኛ የታደሉ ናቸው።

ምንጭ፡ my 67 Moral Story Collections **"The last Ride"** A true story posted by Kent Nerburn ኒው ዮርክ (እ.አ.አ.) 1966 - ዓ. ም. *ሥሙ ባልታወቀ የኒው ዮርክ ከተማ ታክሲ ሾፌር ተፃፈ* * ነሐሴ 2007 ዓ. ም. - አዲስ አበባ






የዚያን እለት ምሽት ወደ ቤት እንደገባሁ ባለቤቴ እራታችንን ስታቀራርብ እጇን ያዝ አደረኩና “የምነግርሽ አንድ ትልቅ ጉዳይ አለኝ” አልኳት። አጠገቤ ቁጭ ብላ በፀጥታ በመመገብ ላይ ሳለች በጨረፍታ ዓይኖቿን ለማየት ሞከርኩ፤ አንዳች ሊገለጽ የማይችል የጉዳት ስሜት ይነበብባቸዋል። ምን ብየ እንደምጀምር ግራ ገባኝ። የልቤ ምት ሲፈጥን ፍርሃት ውርር አደረገኝ፤ ምንም ይሁን ምን በውስጤ የማስበውን የፍቺ ጥያቄ አውጥቼ  መተንፈስ አለብኝ። ለስለስ ባለ አንደበት “አሚ - ትዳራችንን ማፍረስ እፈልጋለሁ”። ነግሬአት አረፍኩ።

ዝምታ . . . በንግግሬ ምንም አይነት የድንጋጤም ሆነ የንዴት ስሜት ሳይታይባት ቆየችና በቀስታ “ለምን ?” ስትል ጠየቀችኝ።

ዝም አልኩ፣ ምን ልበል?። ለጥያቄዋ መልስ ባለመስጠቴ ተናደደች - የምትመገብበትን ሹካ ወረወረችብኝ “አንተ ሰው አይደለህም አውሬ ነህ - አውሬ!” በማለት ጮኸችብኝ። ምንም መነጋገር አልቻልንም፣ ስቅስቅ ብላ ታለቅስና ትወራጭ ጀመር። እንዲህ የሚያደርጋት በትዳራችን ውስጥ ምን ክፉ ዱብ-እዳ እንደገባ ያለማወቋ እንደሆነ ገብቶኛል። የምሰጣት ተገቢና አጥጋቢ ምላሽ ግን የለኝም። እውነታው ልቤ ወደ ውጪ ሸፍቷል። የኔው ቢሮ ሠራተኛ የሆነችው - ጄን ፍቅሯን ነጥቃታለች። ዳግም ላፈቅራትም ሆነ ልገነዘባት እንደማልችል ሆኖ ግንኙነታችን ተበላሽቷል።

ጥልቅ በሆነ የፀፀት መንፈስ አንድ የፍች ሠነድ አዘጋጀሁ። ይኸውም መኖሪያ ቤታችንን፣ መኪናችንን እንዲሁም የኩባንያየን 30 በመቶ ድርሻ ለእርሷ የሚሰጥ ነበር። ይሁን እንጂ በቅጽበት ተመልክታው ወረቀቱን ቀዳዳ ፊቴ ላይ በተነችው። የህይወቷን አስራ አምስት ዓመታት አብራኝ ያሳለፈች ሴት አልመስል አለችኝ፣ በአንዴ ተለወጠች። በክህደት ለተመለሰው  ፍቅሯ፣ ለባከነው ጊዜዋ፣ መና ለቀረው ድካምና ልፋቷ ባዝንም ወደ ኋላ መመለስና ለጄን እንደምወዳት የሰጠኋትን ቃል ማጠፍ የማይሆን ነው። በመጨረሻ ጮክ ብላ አለቀሰች። ይህ ድርጊቷ የምጠብቀው ነበር። እፎይታ ተሰማኝ፣ ለብዙ ሳምንታት በውስጤ ሲብላላ የነበረው የፍች ጥያቄ ቀለል ያለና መስመር የያዘም መሰለኝ።

በማግስቱ እቤት የገባሁት ውድቅት ላይ ነበር። ሳሎን ጠረጴዛ ላይ የሆነ ነገር ትጽፋለች፤ ሰላምታም ሆነ እራት የለም በቀጥታ ወደ መኝታ ክፍሌ ገብቼ ተኛሁ። ወዲያው ጭልጥ ያለ እንቅልፍ ወሰደኝ። ምክንያቱም ከጄን ጋር በነበረን አስደናቂ ውሎ እጅግ ተዳክሜ ነበር። በመሃል ስነቃ የሳሎኑ መብራት እንደበራ ነው። ቀስ ብዬ ተነሳሁና ገርበብ ወዳለው በር አመራሁ፤ በነበረችበት መፃፏን አላቋረጠችም፣ በምን ቸገረኝነት አየት አድርጌአት የተቋረጠ እንቅልፌን ለመቀጠል ተመልሼ ተኛሁ።

ጠዋት በእርሷ በኩል ያዘጋጀችውን የፍች ዝርዝር ሂደት በጽሁፍ አቀረበችልኝ። በሰነዱ ላይ ምንም አይነት ንብረት፣ ገንዘብም ሆነ የኩባንያ ድርሻ እንደማትፈልግ ገልፃ ነገር ግን ከፍችው በፊት የአንድ ወር (የ 30 ቀን) የቅድመ ፍቺ ጊዜ እንደምትሻ አስፍራለች። በዚህ የቅድመ ፍች ማስጠንቀቅያ ወር ውስጥ ሁለታችንም ምንም እንዳልተፈጠረ አስመስለንና ተቻችለን መቆየት እንደሚገባን፤ ምክንያቱም የልጃችን ፈተና በቀጣዩ ወር ውስጥ ስለሆነና በተሰናከለው የኛ ትዳር ምክንያት እንዳይረበሽ በማሰብ መሆኑን ዘርዝራ አስቀምጣለች። እስከዚህ ድረስ ያለው ሃሳብ በእኔ ዘንድ ተቀባይነት አግኝቷል። ይሁን እንጂ የእርሷ ጥያቄ አላበቃም። በተጨማሪ ይላል :- የሰርጋችን እለት ከሚጉላ ክፍላችን እንዴት ተሸክመኸኝ እንደወጣህ ለማስታወስ በቅድመ ፍቺው የ 30 ቀን ጊዜ ውስጥ በየዕለቱ ጠዋት ጠዋት ልክ በዚያን ጊዜ እንዳደረግኸው ተሸክመኸኝ ከመኝታ ቤታችን እስከ መግቢያው በር ታደርሰኛለህ ይላል።

ሴትየዋ ነካ አደረጋት እንዴ? ብየ ባስብም ግድ የለም መጨረሻችንን በመቻቻል ልለፈው በማለት ይህንን ግራ የሚያጋባ ጥያቄ ተቀበልኩት። በባለቤቴ በኩል ስለፍችው የቀረቡትን ቅድመ ሁኔታዎች ለ ጄን ነገርኳት፤ ከትከት ብላ ሳቀችና "ይህንን ሁሉ የማይረባ ነገር ትታ የማይቀረውን ፍቺ ብትጋፈጥ ይሻላታል" አለችኝ የንቀትና የአሽናፊነት መንፈስ እየታየባት።

***<u>የመጀመሪያው ቀን :-</u>***

እኔና ሚስቴ ትዳራችን ውጥረት ውስጥ ከገባ ወዲህ ምንም አይነት የአካል ንክኪ አልነበረንም። የመጀመሪያው ቀን ተሸክሜ ከመኝታ ቤታችን ሳወጣት ሁለታችንም የተጃጃልን መሰልን። ልጃችን ከኋላ ኋላችን ተከትሎ እያጨበጨበ . . . “አባቢ ማሚን ተሸከማት - አባቢ ማሚን ተሸከማት” በማለት በልጅ አንደበቱ እየጨፈረ ያጅበናል፣ ቃላቶቹ ራሴን አሳመሙኝ በማበድ ላይ ያለሁም መሰለኝ። ከመኝታ ቤት ሳሎኑን አቋርጬ እስከ ፊት ለፊቱ በር ድረስ ከአስር ሜትሮች የበለጠ፤ በክንዴ እንደተሸከምኳት ስራመድ አይኖቿን ጨፍና በለሆሳስ እየደጋገመች “ስለ ጋብቻችን መፍረስ በፍጹም ለልጃችን እንዳትነግረው” ትለኝ ነበር። ብስጭቴን ውጬ በእሽታ ራሴን በመነቅነቅ ደረጃው ላይ አስቀመጥኳትና ኮቴን ለብሼ ወደ መኪናየ ሳመራ፤ እሷም ወደ ሥራ የሚወስዳትን ሰርቪስ ለመጠበቅ ወጣች።

***<u>ሁለተኛው ቀን :-</u>***

በሁለተኛው ቀን ሁለታችንም ከትናንቱ በተሻለ ሁኔታ ቀለል ብሎን ነበር። ዘና ብላ ደረቴ ላይ ጋደም አለች። ያ እወደው የነበረ ግሩም መአዛ ሽሚዟን ዘልቆ አፍንጫዬጋ ደረሰ። አምስት ዓመት እፍ ባለ የፍቅር ጓደኝነት፣ አስሩን ደግሞ አብረን በቀለስነው የትዳር ጎጆ አሳልፈን እዚህ ላይ ደርሰናል። አብሮኝ ያረጀው ጠረኗ በትውስታ ወደ ኋላ ሰቅዞ ያዘኝ . . . ይህችን አሁን በክንዶቼ መሃከል አጥብቄ የያዝኳትን ሴት ለረጅም ጊዜ ትኩረት እንደነፈኳት ታወቀኝና መደበቅያ እስካጣ በራሴ አፈርኩ!።

***ሦስተኛው ቀን ፦***

በሦስተኛው ቀን ትኩር ብየ አየኋት፣ በማይጠበቅ ፍጥነት አረጀችብኝ። ዳግም ወጣት መሆን አትችልም፣ ፊቷ በጥቃቅን መስመሮች መሸብሸብ ጀምሯል፣ ፀጉሯን ሽበት እየወረረው ከፊሉ ገብስማ ሆኗል፣ ሁሉንም ነገር ለጎጆዋ ስትል አጥታለች። የዘመመው ትዳራችን አንድም ሳያስቀር ቀምቷቷል እኔስ ምን አደረኩላት? የሚል ሃሳብ ሸውው አለና ለሰከንዶች ብዥታ ውስጥ ከተተኝ።

***አራተኛው ቀን ፦***

በአራተኛው ቀን ጎንበስ ብየ አቅፌ ሳነሳት የነበረን ጽኑ ቅርበት በትዝታ አንሳፈፈኝ፣ ህሊናዬ ይህች ናት የህይወቷን አስራ አምስት ዓመታት ለአንተ የሰጠችህ - ባተሌ ሴት፤ አንተ ግን ረክሰህ አረከስካት፣ ንጹህ ፍቅሯን ማጥ ውስጥ ወርውረህ በጭቃ ለወስከው፣ ውለታዋን ጥላሸት ቀብተህ በክህደት ከፈልካት . . . እያለ በፀፀት ይለበልበኝ ጀመር። ምን ልሁን?።

***አምስተኛውና ስድስተኛው ቀን ፦***

በአምስተኛውና በስድስተኛው ቀናት ቅርርባችን ዳግም ነብስ እየዘራና እያደገ እንደመጣ ተሰማኝ። በማላውቀው ሁኔታ እፍረቴና መፀፀቴ እየቀነሰ ሙሉ አይኗን ማየት ቻልኩ። ምናልባት ውስጤ ጥፋተኛነቱን እያመነና በየእለቱ መገናኘታችን ሃዘኔታን ስለጫረብኝ ይሆናል። ወደ እሷ ስሄድ፣ ስሸከማትና ስራመድ ሁሉ ዘና እያልኩ በመምጣቴ የተቀሩት ቀናት ቀላልና የማያውኩ ሆኑልኝ፣ በዚህ ሁኔታ ይበልጥ ጥንካሬ ስለተሰማኝ በተሻለ መንፈስ ቀጠልኩበት። ይህንን ክስተት ግን ለጂን አልነገርኳትም።

***ወደ መጨረሻው በአንዱ ቀን ፦***

ወደ መጨረሻው በአንዱ ቀን የምትለብሰውን ልብስ በመምረጥ ቆየች፣ ትለካለች - ታወልቃለች፣ ትለካለች - ታወልቃለች የሚሆናትን አላገኘችም። በረጅሙ ተነፈሰችና ቀና ብላ እያየችኝ . . . "ቀሚሶቼ ሁሉ ሰፉኝ" አለች። ወዲያውኑ አንድ ነገር ተገነዘብኩ! ሰውነቷ በፍጥነት እየቀነሰ ነው። ለካስ በቀላሉ እሸከማት የነበረው ለዚህ ነው?። ስለ ብዙ ነገሮች አሰብኩ፤ ሁኔታዋ በቅጽበት አእምሮየን ነካው። አያሌ መከራዎች በውስጧ ተቀብረዋል፣ ልቧ በርካታ ምሬቶችን ተሸክሟል፣ እያደረኩ ያለሁት ሁሉ ለእርሷ አይገባትም፤ ምስኪን . . . በደመነፍስ ብድግ ብየ አቀፍኳት ፊቷን፣ ራስዋን፣ እጆቿን ደባበስኩ - መላ አካሌ በቁጭት ወላፈን ተለበለበ፤ አፌን እሬት እሬት አለኝ፤ አፈርኩ፣ ተሸማቀቅሁ . . . እንደብርድ አንዘፈዘፈኝ።

"አባቢ! አባቢ! ማሚን የምትሸከምበት ሰአት እኮ ደርሷል?" የሚለው የልጃችን ድምጽ ነበር ከገባሁበት ጥልቅ የፀፀት ባህር መንጥቆ ያወጣኝ። የአባቱ በየቀኑ እናቱን እየተሸከመ ወደ ውጪ ማውጣት ለእርሱ በየእለቱ የሚከናወን አንድ ጉዳይ ሆኖ ታይቶት ነበር። እናቱ በምልክት ጠራችው፤ ሄዶ አንገቷ ስር ሽጉጥ አለ - አቀፈችው . . . ስፍስፍ ብለው ተቃቀፉ። ፊቴን ወደ ሌላ አቅጣጫ አዞርኩ፣ እንደ ጉድ የምፈራው የጥፋተኝነት መንፈስ ሸንቆጥ አድርጎኝ አለፈ። በዚህች የመጨረሻ ደቂቃ ሃሳቤን ልቀይር እንደምችል ታወቀኝ። ቀስ ብዬ በክንዶቼ አነሳኋትና ተሸከምኳት . . . ከመኝታ ቤት ሳሎናችንን አቋርጠን እስከ ዋናው በር፣ እጆቿ በአንገቴ ዙርያ ተጠምጥመው፣ ጥብቅ አድርጌ እንዳቀፍኳት ስራመድ ሁኔታው ሁሉ ልክ የሠርጋችን እለት እንደነበረው ነበር ።

***የመጨረሻው ቀን ፦***

እየቀለለ የመጣው ክብደቷ ሃዘን ውስጥ ከቶኛል። በመጨረሻው እለት ተሸክሜ ስወስዳት አንድ ታላቅ እርምጃ መውሰድ እንዳለብኝ ተረዳሁ። ልጃችን ወደ ትምህርት ቤት ሄዷል። ውስጤ ለመግለጽ በሚያዳግት አዲስ መንፈስ ሲሞላ የማላውቀው ደስ የሚል ብርታት ተሰማኝ። በጥንቃቄ አንስቼ ተሸከምኳት፣ ወደ ደረቴ አስጠግቼ አቀፍኳትና በዝግታ እየተራመድኩ "ውዴ እውነት - እውነት እልሻለሁ ትዳራችን ይህን ያህል መሳሳቱንና የቅርብ እሩቅ መሆናችንን አልተረዳሁም ነበር" አልኳትና መቀጠል አቃተኝ። ለመናገር ያሰብኩት . . . ብዙ ነበር። ውስጤን "አሁን የተግባር ጊዜ ነው" አልኩትና ግንባሯን ስሜ የተለመደው ስፍራ ላይ አስቀመጥኳት።

የሚባክን ጊዜ የለም . . . መኪናዬን አስነስቼ በፍጥነት ወደ ቢሮ ነዳሁ። ምንም አይነት መዘግየት ውሳኔዬን እንዳያስቀይረኝ ስለሰጋሁ በሬን እንኳን ሳልዘጋ እየተቻኮልኩ ደረጃውን ሽቅብ በሩጫ ወጣሁና የጂንን ቢሮ አንኳኳሁ። እንደከፈተችልኝ ፊት ለፊት እያየኋት "አዝናለሁ ጂን - የፍችውን ጉዳይ ሰርዤዋለሁ፣ ትዳሬን አላፈርስም!" አልኳት። ትኩር ብላ አየችኝ፣ ባልተጠበቀው ሁኔታየ ደንግጣለች። እጇን ዘርግታ ግንባሬን እየዳሰሰች "ሰውነትህ ያተኩሳል ልበል?" አለችኝ። እጇን ከግንባሬ ላይ ገፍቼ "አዝናለሁ ከእንግዲህ ሚስቴን አልፈታም፤ ለጋራ ህይወታችን ትኩረት በመንፈጋችን እንከን አልባው ትዳራችን ተናግቷል። ዳግም ስለመፋቀር አለመፋቀር ሳይሆን ዋናው ጉዳይ እኔ በፈፀምኩት ያልተገባ ድርጊትና ሃጥያት ቤተሰቦቼን ማሰቃየቴ ነው። እውነቱን ለመናገር በትክክል እንደተገነዘብኩት ከሆነ በውላችን መሠረት "ሀ" ብዬ እንደ ሠርጋችን እለት ቤታችን ውስጥ እሷን መሸከም ከጀመርኩባት ቀን ወዲህ እስከ እለተ ሞቴ ልሸከማትና ልንከባከባት እንደሚገባኝ በብርቱ አምኛለሁ!"። አልኳት ።

ጀን ከእንቅልፉ እንደባነነ ሰው በረገገች። ተንጠራርታ ክፉኛ በጥፊ መታቸኝና በሩን ላዩ ላይ ወርውራ ዘጋችው። በሆዴ "ሲያንሰኝ ነው" አልኩና ቁልቁል ደረጃውን ወርጄ መኪናዬን እያስሽከረከርኩ ወጣሁ። አደባባዩን አልፌ ከዋናው ጎዳና በስተቀኝ አበባ መሸጫው ሱቅ ፊት ለፊት አቆምኩና ወደ ውስጥ ግብቼ እቅፍ አበባ አዘዝኩ።

አበባውን ያቀረበችልኝ የሽያጭ ሰራተኛ "በካርዱ ላይ ምን እንዲፃፍሎት ይፈልጋሉ?" ስትል ጠየቀችኝ። ፈገግ ብዬ ካርዱን ተቀበልኳትና እንደዚህ ፃፍኩበት፡- "ውዴ! ይቅርታ! ከዚህች ዓለም በሞት እስከምለይ ድረስ በየእለቱ ጠዋት - ጠዋት እንደ ሠርጋችን እለት እቅፍ አድርጌ - ተሸክሜ አብሬሽ ... እኖራለሁ። እንለያይም እወድሻለሁ!" ጽፌ እንደጨረስኩ ካርዱን ፖስታው ውስጥ ከትቼ አበባው መሃል ላይ ሰካሁት።

## የመጨረሻው መጨረሻ ፡-

ወትሮ ሃሳብ ሲገባኝ እንደማደርገው፣ የምወዳትን ሙዚቃ በፉጨት እያዜምኩ ወደ ቤቴ ገሰገስኩ። ቀልድ የለም እርኩሰቴን በንሰሃ ፀበል ለማጠብና እኔነቴን በይቅርታ መንፈስ ለማደስ ጊዜው አሁን ነው። ለባለቤቴ የገዛሁትን እቅፍ አበባ በጉያዬ፣ እፀ አልባ የህይወት እቅዴን በልቤ ይዤ በፍጹም እርጋታና ጉጉት ደረጃውን እየተራመድኩ ውዷን የልጅነት ሚስቴን፣ የትዳሬን አጋር . . . አልጋዋ ላይ እንደተኛች ላስደንቃት መኝታ ቤቱን ከፍቼ ገባሁ።

አዎን - አገኘኋት፤ ለጥ ብላ ተኝታለች "አሚ! - አሚ!" ጠራኋት . . . ተኝታለች። ዳግም ላለመንቃት ተኝታለች፣ አሚ የዘላለሟን አንቀላፍታለች፤ አርፋለች። ምን ይዋጠኝ? ምን ልሁን? እጄ ላይ የቀረው በምንም የማልመልሰው ደረቅ ፀፀትና አበባው ብቻ ነው።

ባለቤቴ ለወራት ያህል ከካንሰር ጋር ተጋፍጣለች። እኔ ግን ከጄን ጋር ስቃበጥ ጉዳትዋን ለማየት አልታደልኩም። በቅርብ እንደምትሞት ተነግሯታል አውቃዋለች። ነገር ግን እኔን ከማንኛውም ክፉ ገጠመኝና የዘላለም ፀፀት ለማዳን እንዲሁም በቀሪው ጊዜ ከልጄ ጋር የሚኖረን ግንኙነት የደፈረሰ እንዳይሆን፣ ቢያንስ ቢያንስ ፍቺውን ብገፉበት እንኳን በልጄ ህሊና "እኔ ሚስቱን አፍቃሪ - ባል ለቤተሰቡ የሚኖር - አባት" እንደሆንኩ ለማስቀመጥ ወደር የለሽ የጽድቅ ተግባር ፈፀመች።

## ፍሬ ~ ሥነ ምግባር ፡-

ወዳጆቼ! ጓዳችን አልተመረመረም እንጂ እንዲህ ከጋብቻው ቁጥር ጋር በሚገዳደር መጠን የሚፈርሰው ጎጆ፣ የሚበተነው ቤተሰብ፣ በየሸንጎው ላይ የሚቀደደው የሰማንያ ወረቀት ሁሉ መንስኤው ቢበረበር እዚህ ግባ የማይባል የጥቃቅን ክፍተቶች ድምር ነው። ሌላው ያልለየለት ሳይፈርስ የተናደ ትዳር ደግሞ የስንቱን አዛውንት ጊዜና ድካም መና እያስቀረ፣ ሲጠገን ደህና እየመሰለ ሲሰበር ውስጡን በጭቅጭቅ እየታመሰ፣ ለስሙ በቆመ ጣራ ሥር አልጋና ልቦችን ለያይቶ በልጆች አስተዳደግና መሰረታዊ ባህሪይ ላይ ሳይቀር ጥቁር ሳንካ የሚጥል የኑሮ ደዌ የስንቱን ትዳር እንደፈታ ቤቱ ይቁጠረው። ጥቃቅን የምንላቸው የህይወታችን የእለት ተእለት ጉዳዮች በእርስ በርስ ግንኙነታችን ውስጥ ወሳኝ ሚና አላቸው። ሃብት፣ ንብረት፣ በባንክ የተከማቸ ገንዘብ . . . ወዘተ ሁሉም ደስታን ለማግኘት ተጨማሪ ግብአቶች እንደሆኑ እንጂ በራሳቸው ዘላቂ ደስታና ትርጉም ያለው የኑሮ ፍስሃ አይሆኑም። ስለዚህ ለትዳር አጋሮቻችን መልካም የጓደኝነት ጊዜን በማመቻቸት፣ ጥቃቅን የመሰሉንን ነገሮች ሁሉ በመገላለጽና በመነጋገ፤ር ትዳራችን በጥልቅ ግንኙነት ላይ የተመሰረተና መተማመን የሰፈነበት ዕውነተኛ ጎጆ ይሆን ዘንድ ምንም ክፍተት አንስጥ።

ምንጭ ፡- የሥነ ምግባርና ቀስቃሽ ጽሁፎች ድረ ገጽ
RayPoffs - http://t.co/zkxqcntrem "Marriage" or "Until Death do us Apart"

● ይህ ከላይ ያነበባችሁት ልብ የሚነካ ታሪክ (እ.አ.) በ 2003 ዓ. ም. ማሌዥያ ውስጥ ለሚገኝ አንድ የዜና አገልግሎት ድርጅት "30 DAYS OF CARRYING MY WIFE" (ሚስቴን የተሸከምኩባቸው ሰላሳ ቀናት) በሚል ርእስ (ኢ - ሜይል) ሲደረገለት የባለታሪኩም ሆነ የፀሃፊው ስም አልሰፈረበትም ነበር። ከወዲሁም ከ2004 ጀምሮ በተለያዩ ማህበራዊ ድረ ገጾች ላይ ሲነበብ ቆይቶ በ 2007 ገደማ የታሪኩ ከፊል ጭብጥ የተካተተባቸው ሁለት ፊልሞች ተሰርተውበታል።

● አንዳንድ ታሪኮች አእምሯችን ውስጥ ይሰነቀሩና ዘወትር ይታወሳሉ፣ ይህ ከወራት በፊት ያነበብኩት ታሪክም ከመሳጭነቱ ባሻገር ትዳርን ላልሞከሩ፣ በትዳር ውስጥ ላሉ፣ ለዘመመባቸውም ሆኑ በተለያየ ምክንያት ለፈረሰባቸው፤ ቀላል የሚመስሉ ነገር ግን ወሳኝ አበርክቶ ያላቸው የውስጥ ጉዳዮች ለቀና ትዳር ምን ያህል ወሳኝ እንደሆኑ ጥልቅ ትምህርት የፈነጠቀ ይመስለኛል።

ሰኔ 2007 ዓ/ም - አዲስ አበባ



## <u>“የሽማግሌው ጫማ”</u>

የከተማውን ጥግ ይዞ በተቆረቆረው ነባር መንደር ውስጥ ለረጅም ጊዜ የኖሩት ሽማግሌ የመጀመርያዋን አውቶብስ ለመያዝ በማለዳ ተነስተው ይጠባበቃሉ። አውቶብሷ እንደመጣች ከሌሎች ተሳፋሪዎች ጋር ተቀላቅለው ለመግባት ቢሞክሩም አቅማቸው ስላልቻለ ወደኋላ እየተገፉ የመጨረሻ ለመሆን ተገደዱ። እንደምንም ታግለው በመግባት መወጣጫ ደረጃውን ለመርገጥ ሲሰናዱ ያልገባ እግራቸውን የሚዘጋው በር ደረሰበትና ጫማቸውን ይዞ ወደውጭ አስቀረባቸው።

የአንድ እግራቸውን ጫማ ተለይተው ወደ ውስጥ የዘለቁት ሽማግሌ ፈጠን ብለው እግራቸው ላይ የቀረውን ጫማ በማውለቅ በአውቶብሱ መስኮት ወደ ውጪ ወረወሩትና ወንበሩ ላይ ተመቻችተው ተቀመጡ። በዚህ መሃል ሁኔታውን ይከታተል የነበረ አንድ ወጣት ቀረብ አለና “ጤና ይስጥልኝ አባቴ፤ ጫማዎን በሩ ይዞ ሲያስቀርቦት አይቼ ነበር፣ ወዲያው ደግሞ እግርዎ ላይ የቀረውን አንድ ጫማ አውልቀው ወረወሩት ይህንን ለምን እንዳደረጉ አልገባኝም?" በማለት ጠየቃቸው።

“ልጄ አንድ ሰው የሚያስፈልገው ጥንድ ጫማ ነው። በሩ ያስቀረብኝን ጫማ ደግሜ አላገኘውም እግሬ ላይ የቀረው ጫማም ብቻውን አያገለግለኝም። ስለዚህ እግሬ ላይ የቀረውን ጫማ በመወርወሬ ማንም ይሁን ማን ያገኛቸው ሰው ሊጠቀምባቸው ይችላል" በማለት ረጋ ብለው መለሱለት። ልጁም በአስደናቂ መልሳቸው መርካቱን በመግለጽ አመስግኗቸው ወደ ቦታው ተመለሰ።

እንደ ሽማግሌው የህይወትን መሰረታዊ የፍልስፍና ጥበብ የተረዳ የለም። ለሌሎች ብንሰጥ የሚጠቀሙባቸው ነገር ግን የኛ ስለሆኑ ብቻ ያለምንም አገልግሎት ያስቀመጥናቸው ምን ያህል እቃዎች እንዳሉን አስበን እናውቃለን?። በየጊዜው የተለያዩ ነገሮች ሊጠፉብን ይችላሉ። በመጥፋታቸው እንደተበደልን ቆጥረን ልንበሳጭ እንችላለን። እስቲ በሌላ መንገድ እንየው - መጥፋት፣ መበላሸት፣ መሰበር ወይም ማለቅ ባይኖር በህይወታችን ውስጥ አዳዲስ ለውጦች በምን መንገድ መከሰት ይችሉ ነበር?።

የሽማግሌውን ድርጊት ሳነብ ራሴን በእርሳቸው ቦታ አስቀመጥኩና ምን አደርግ እንደነበር አሰብኩ። ለእናንተም እንድታስቡበት ጥቂት ሰከንዶች ልስጣችሁና አስቡበት . . . ። በጀ! - እንደሽማግሌው የምታደርጉ ካላችሁ በእውነት የብሩህ አእምሮ ባለቤት ስለመሆናችሁ አትጠራጠሩ። እኔ ግን በአንድ እግር ጫማ የአውቶብስ ጉዞዬን አጠናቅቅና በመልሴ ረከስ ያለ ነጠላ ጫማ ገዝቼ ባለ አንድ እግር ጫማዬን በአዲሱ ነጠላ ጫማ የላስቲክ ከረጢት ውስጥ በመክተት አንጠልጥየው ቤቴ እንደምገባ እርግጠኛ ነኝ።

ልዩነታችን እዚህ ላይ ነው። ወዳጆቼ፡- በየጓዳችን የተከማቹ እቃዎች ሁሉም እንደሚጠቅሙንና እንደሚያስፈልጉን ምን ያህል እርግጠኞች ነን?። እስቲ ዞር ዞር ብለን በየአቅጣጫው እናማትር? አሮጌ ጫማዎች፣ ልብሶች፣ የተለያዩ ቁሳቁሶች፣ ያገለገሉ የቤት እቃዎች፣ የወረቀት ክምር፣ ሰባራ ሰንጣራ . . . የኮተት መአት። የመኖርያ ስፍራ ጥበት ያለብን ቢሆን እንኳ ሻንጣዎቻችን፣ የቁም ሣጥንና የጠረጴዛ መሳቢያዎቻችን፣ የአልጋችን ሥርና የኪስ ቦርሳችን ሳይቀር አጓጉል አብጦ ቅርጹ እስኪቀየር የጠቀጠቅነው ቅራ ቅንቦ ሁሉ እውን ጠቃሚ ነው?።

በየጊዜው የማንጠቀምባቸውን ነገሮች የመጣል ልምድ የለንም። አዳዲስ እቃዎች ስንገዛ አሮጌውን በተለያየ መንገድ ከማስወገድ ይልቅ ምናልባት ሊያስፈልገን ይችላል በሚል የሩቅ ግምት ዞር አድርገን ማከማቸት ይቀናናል። በቅርስነትና በጥንታዊ የመገልገያ መሳርያነት ለታሪክ የሚፈለጉት ደግሞ ሁለት ሦስት ሺህ ዓመታትን ያስቆጠሩ የወግ እቃዎች እንጂ የአያቶቻችንን አልጋ፣ የቅድም አያቶቻችንን እንሥራ፣ የአባቶቻችንን ጠረጴዛና የራሳችንን አሮጌ ጫማዎች አጠራቅመን እንደ ድንቃ ድንቅ ቁሳቁሶች መጠበቅ ያለብን አይመስለኝም።

እንደሽማግሌው የማይጠቅመንን እንጣል፣ በየወቅቱ የማንሻውን እየለየን እናስወግድ። ለእኛ ምንም ካልፈየዱ ሌሎች እንዲጠቀሙበት በቀና መንፈስ መፍቀድ በራሱ ጥሩ ሰውነት ነው። ጥሩ ሰው (መልካም ሰው) ደግሞ እንኳን የማይፈልገውን የሚያስፈልገውንም የሚከለክል ንፉግ አይደለምና እናስብበት።

ምንጭ፡ WWW.Roger Darlington's World - thoughtful stories
"THE OLD MAN AND HIS SHOE”
ሃምሌ - 2007 *** አዲስ አበባ



## ያልተገደበ ፍቅር
**("ጓደኝነት - 2")**

ታሪኩ በቬትናም ጦርነት ወቅት ለሃገሩ አሜሪካን ተሰልፎ ስለተዋጋ አንድ ወታደር ነው። አሜሪካዊው ወታደር በጦርነቱ ማብቂያ ግድም ለአመታት ከቆየበት የጦር ግንባር ግዳጁን አጠናቆ ወደ ቤቱ ለመመለስ በመንገድ ላይ ነበር። ሳን ፍራንሲስኮ እንደደረሰ ለረጅም ጊዜ ወደተለያቸው ቤተሰቦቹ ስልክ ደወለ፤ አባትና እናት የብቸኛ ልጃቸው ናፍቆት ሲያብሰለስላቸው ከርሟልና ደስ አላቸው።

"ሃሎ እማማና አባባ እንደምናችሁ? ይኸው ጦርነቱ አበቃ ወደ ቤት ልመጣ ነው"

"ደህና ነን ልጄ፤ እንኳን ለዚህ አበቃህ ናልን - ናልን እንጠብቅሃለን" አባት መለሱ።

"አመሰግናለሁ፤ አንድ ውለታ ልጠይቃችሁ ነው። ጓደኛዬ ከኔ ጋር አለ፣ ወደ ቤት ይዤው ልመጣ ፈልጌአለሁ"

"አ ው! ምንም አታስብ፣ ደስ ይለናል ይዘኸው ና" መለሱለት።

"ግን ማወቅ ያለባችሁ አንድ ነገር አለ" ልጅ ንግግሩን ቀጠለ . . . "ጓደኛየ በውግያው ወቅት ክፉኛ ጉዳት ደርሶበታል። የተቀበረ ፈንጂ ባደረሰበት አደጋ የቀኝ እጁንና የግራ እግሩን አጥቷል። ምንም መጠግያና የሚሄድበት ቦታ የለውም እናም ወደዛ አምጥቼው አብሮን እንዲኖር እፈልጋለሁ" አላቸው።

በሁለቱም በኩል ፀጥታ ሰፈነ። አባትና እናት በዓይናቸው ተነጋገሩ። ከጥቂት ሰከንዶች በኋላ "በሰማነው ነገር በጣም አዝነናል! ምናልባት የሚኖርበትን ቦታ በመፈለግ ልንረዳው እንችላለን" በማለት መለሱለት።

"አባዬ እና እማዬ – አይሆንም! እኔ የምፈልገው ከእኛ ጋር አብሮን እንዲኖር ነው!" አላቸው።

"ውድ ልጄ" አሉ አባት "ምን እየጠየከን እንደሆነ በሚገባ የተረዳኸው አይመስለኝም። አንድ የአካል ጉዳተኛ ሰው ሊያሳድርብን የሚችለውን አስቸጋሪ ጫና ማወቅ አለብህ። እኛ በራሳችን የምንኖረው ህይወት አለን፣ እንደዚህ ያለ በእለት ተእለት ኑሯችን ውስጥ ጣልቃ የሚገባ ነገር አንፈቅድም። የጓደኛህን ነገር እርሳውና አንተ ብቻ ና። ስለ ወደፊት ህይወቱ ማቀድና የአኗኗር መንገዱን ማዘጋጀት ያለበት እሱ ራሱ ነው" በማለት መለሱለት።

በዚህች ቅጽበት ቀጨጭ የሚል ድምጽ ተሰማ፤ ልጁ ስልኩን ዘጋው። ከዚያ ወዲህ አባትና እናት ከልጁ ምንም ቃል አልሰሙም። በተደጋጋሚ በስልክ ለማግኘት ያደረጉት ሙከራም አልተሳካም። ቀናት አለፉ፣ ምንም የለም። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ አንድ ቀን ጠዋት ከ ሳን ፍራንሲስኮ ፖሊስ ስልክ ተደወለ . . . የጦር ሰራዊቱ ባልደረባ የነበረው ልጃቸው ከረጅም ሕንፃ ላይ ወድቆ ህይወቱ እንዳለፈ መርዶውን አረዷቸው። ደዋዩ ሰው እንደ ፖሊስ እምነት አደጋ ሳይሆን ሆን ብሎ ህይወቱን በገዛ እጁ ለማጥፋት የፈፀመው እንደሆነ እንደሚጠራጠሩና ቀጣይ ምርመራም በማድረግ ላይ መሆናቸውን ጠቅሶ መጥተው እንዲለዩት በነገራቸው መሰረት ሃዘን መሪር በትሩን ያሳረፈባቸው አባትና እናት ተያይዘው ወደ ሳንፍራንሲስኮ በረሩ።

ሳንፍራንሲስኮ አውሮፕላን ማረፍያ የጠበቃቸው የፖሊስ መኮንን በቀጥታ ወደ ከተማው አስከሬን ማቆያ ሥፍራ ወሰዳቸውና መሳቢያውን ከፍቶ አስከሬኑን አሳያቸው፤ አረጋገጡለት። በትክክል እሱ ነው። ተንሸራታቹ ቃሬዛ ላይ ፀጥ ብሎ በጀርባው የተኛውና ፊቱ ላይ የተረጋጋ ፈገግታ የሚነበብበት፣ በቬትናም ጦርነት ግዳጁን በብቃት የተወጣ ጀግና . . . ብቸኛ ልጃቸውን ትኩር ብለው አዩት። በእንባ ጭጋግ ተከበው፣ ልቦቻቸው በፀፀት እንደተኮማተሩ በደንብ አስተዋሉት። ያላወቁትን አስፈሪ እውነታም አሁን ተገነዘቡ። ልጃቸው - ውዱ ልጃቸው . . . አንድ እጅና አንድ እግር ብቻ ነበረው።

= = = = ✱ ✿ ❀ ❀ ✿ ✱ = = = =

ምስኪን አባትና እናት በፍጹም አይፈረድባቸውም። ጓደኛህን ይዘኸው ና አለማለታቸው እንደ ጥፋት ይቆጠርባቸዋልም አልልም። ጨርሶ የሁላችንም እናትና አባት ከዚህ የተለየ መልስ ይሰጣሉ ብየም አላምንም። ለምን? ግን ለምን?። ሰው ስለሆንን!። በራሳችን የኑሮ ውጣ ውረድ የተጠመድን፣ እጅግ በርካታ ጥንድ ጥንድ ባህሪያት እነ ጽድቅና ኩነኔ፣ ደግነትና ክፋት፣ እውነትና ሃሰት . . . ወዘተ ድብቅና ግልጽ ስሜቶች በተቃራኒ አቅጣጫ የሚጎትቱን ሰዎች ስለሆንን። ከማንም በላይ እራሳችንን የምንወድ ፍጡራን ስለሆንንም ይሆናል . . . ሌላም ሌላም።

ሁላችንም አብረውን እንዲሆኑ የምንፈልጋቸውና የምንወዳቸው ሰዎች የትኞቹ ናቸው?። ጥሩ መስለው የሚታዩን፣ ደስታን ሊፈጥሩልን ይችላሉ ብለን የምንገምታቸውን፣ ይጠቅሙናል አልያም በራሳችን መስፈርት ይመጥኑናል ብለን የምናስባቸውን . . . እንጂ፤

ከኛ ጋር መሆናቸው ምቾት ይነሳናል ወይም ያስቸግሩናል ብለን የምንጠራጠራቸውን ሰዎች መች እናቀርባለን?። እንደውም እውነቱን ለመናገር አካልና ጤናቸው የተጓደለ፣ ችግርና ጉስቁልና የተጫናቸው ወይም ቆንጆና መልካም መሆናቸው በእይታ ብቻ ካልተመቸን እንዳይቀርቡን እናደርጋለን አልያም በተቻለን መጠን እንሸሻቸዋለን ሃቁ እንግዲህ ይኸው ነው።

መከፋታችንን የምናዋየው፣ አለም በተደፋብንና ከፉ ጨለማ በዋጠን ሰዓት የምንሸሸበት፣ ከነስንክልናችን ሳይፀየፍ የሚቀበለንና ያልተገደበ ፍቅር የሚለግሰን አንድ ሰው፣ ባለቀ ሰአት ሮጠን የምንገባበት የተከፈተ በርና የተወዳጅ ቤተሰብ ልብ ባይኖረንስ? ምን ይሰማናል?። ራሳችንን በተገፉና የሰው ያለህ በሚሉ ምንዱባን ቦታ አድርገን እንይ። ይህ የሰው ልጆች የጋራ ባህሪይ ችግር ነው።

እስቲ ዛሬ ማታ ከማሸለባችን በፊት በዘወትር የምስጋና ወይም የዝሁር ፀሎታችን ላይ ይህቺን ጥቂት ቃል እናክል።

<u>“አምላክ ሆይ ! በሰዎች መሃከል ምንም ልዩነት ሳላደርግ ባሉበት ሁኔታ እንድቀበላቸው፣ እንድወዳቸውና ያልተገደበ ፍቅር እንድለግሳቸው እችል ዘንድ ብርታትና ጥንካሬን ስጠኝ - አሜን”</u>

ወዳጆቼ :- አንድ እጅግ ታላቅ ተአምር አለ . . . **<u>ጓደኝነት</u>** ይባላል። እኩል የተለገሰን በልባችን ውስጥ መኖሩንም ሆነ መቼ እንደሚፈነዳ የማናውቀው እንቡጥ አበባ። ልዩና ተአምረኛ ውጤቱ የሚገለፀው ድንገት ከቁጥጥራችን ውጪ በውስጣችን ተሰራጭቶ ሰብአዊ ፀጋ ሲያላብሰንና ሌሎችን በመውደድ በጎ እንድንሰራ ሲያደርገን ብቻ ነው። ለዚህ ነው ጓደኝነት ከፈጣሪ የተበረከተልን ከድንቅም ድንቅ ተአምራዊ ስጦታ ነው የሚባለው። በእርግጠኛነት ጓደኞቻችን በዋዛ የማይገኙ ውድ ጌጦቻችን ናቸው። ደስተኛ እንድንሆን ፈገግታ ይለግሱናል፣ እንድንበረታና ለስኬት እንድንበቃ ይደግፉናል፣ ጆሯቸውን ሰጥተው ያዳምጡናል፣ ምክራቸውን አካፍለው ያርቁናል (ይጠብቃል)። ከማንም ከምንም በላይ ዘወትር ልባቸውን ከፍተው ይጠብቁናል። ትክክለኛው የጓደኝነት ወግ ይህ ነው።

ዛሬ ዛሬ የጓደኝነት ትርጉሙ ተፋልሶ፣ አለቅጥ ተዋርዶና አዋዋሉ ረክሶ ከሥሙ በስተቀር መላ ይዘቱን አጥቶ እርቃኑን ቆሞ እያስተዋልነው ነው። በስሙ እየተሸቀጠ አጓጉል ባክኖ ሊጠፋ አንዲት ጀምበር ብቻ የቀረው፣ እንጥፍጣፊ ጉልበቱን ተሰልቦ እስከወዲያኛው ሊሰናበተን መቃብሩ አፋፍ ላይ የቆመ ምስኪን ሆኗል። እናንተየ - በድሮው ጓደኝነት ይገርችኋለሁ!። ሥሙን ብቻ ትቶልን ለዘላለሙ ሳይሰናበተን በፊት እጁን ይዘን ወደቦታው እንመልሰው ሥሙ ምንም አይፈይድልንም። ሥምማ ሥም ብቻ ነው - ባዶ ነተራ።

አመሰግናለሁ! ፀሎትዋን አንርሳ።




ምንጭ : የሥነ ምግባር ጽሁፎች ድረ ገጽ - www.Livin3.com
Motivational and Inspiring Short Stories ርእስ :-”UNCONDITIONAL LOVE”
ደራሲ : ያልታወቀ * ሚያዝያ 2007 * አዲስ አበባ



**"የቶማስ እናት"**

ጊዜው (እ.አ.አ.) በ 1854 አሜሪካ - ፖርት ኸረን፣ ሚቺጋን ውስጥ ነው። ለቤተሰቦቹ ሰባተኛና የመጨረሻ የሆነው የስምንት አመቱ ታዳጊ ቶማስ ቀትር ላይ ከትምህርት ቤቱ ሲመለስ በእጁ አንድ የታሸገ ፖስታ ይዞ ነበር። ጓዳ ወደነበረችው እናቱ ሄደና ፖስታውን ሰጣት። አያይዞም መምህሩ ለእናቱ ብቻ እንዲሰጥ አበክረው መናገራቸውን ገለፀላት። እናቱ አጠገቡ እንደቆመች ፖስታውን ከፍታ ታነብ ጀመር . . .። ፊቷ ቅጭም እንዳለ ቢሆንም የአይኗ መደፍረስ ግን የስሜቷን መታወክ ያሳብቃል። አንብባ እንደጨረሰች ፈገግ ብላ ወደ ልጇ ዞረች።

በጉጉት ያፈጠጠው ልጅ ቀና ብሎ "ምንድነው? ምን ብለው ነው የፃፉት?" ጠየቃት።

"ልጅሽ እጅግ በጣም ጎበዝና አስተዋይ ነው። ትንሿ ትምህርት ቤት አትመጥነውም፣ የሚያስለጥኑት ጥሩ ጥሩ እውቀት ያላቸው መምህራን ስለሌሉን እባክሽ አንቺ ብታስተምሪው ይሻላል" በማለት አነበበችለት።

አመታት ተቆጠሩ፣ የቶማስ እናትም አርጅታ ካረፈች ብዙ ጊዜ ሆናት። የአለማችን ወደር የለሽ ሳይንቲስትና ተመራማሪ ቶማስ ኤድሰን ከአምፖል እስከ ተንቀሳቃሽ ምስልና የኤሌክትሪክ ባትሪን ፈጠረ። በዚህ አላበቃም በ 20 ኛው ክፍለ ዘመን ከሰዎች የእለት ተእለት ሕይወት ጋር በቅርብ የተያያዙ 1093 ግኝቶችን በባለቤትነት ያስመዘገበ ጠቢብ ሆነ። ከእለታት በአንዱ ቀን ወደ ድሮ ቤታቸው ሄዶ አንዳንድ እቃዎችን ሲፈልግ ቁም ሳጥኑ ውስጥ ከመደርደርያው ጥግ ላይ አንድ የተጣጠፈች ደብዳቤ አየና አነሳት። ያኔ ትንሽ ልጅ እያለ አስተማሪው ለእናቱ እንዲሰጥ የላካት ፖስታ ነበረች።

ከፍቶ ያነባት ጀመር "ልጅሽ ቶማስ የአእምሮ ዘገምተኛ ነው። ለእርሱ የሚሆን ቦታ ስለሌለን ከዛሬ ጀምሮ ከትምህርት ቤቱ አባረነዋል" ትላለች።

አንብቦ እንደጨረሰ መሬተት ላይ ወድቆ እንደ ልጅነቱ፤ እየተንፈራፈረ አለቀሰ። ከዚያም የእለት ውሎ መመዝገቢያውን አወጣና "ቶማስ አልቫ ኤድሰን የአእምሮ ዘገምተኛና የማይጠቅም ተብሎ የተባረረ ህፃን ነበር፤ እናቱ ግን ወደ ክፍለ ዘመኑ ምርጥ ሊቃውንትነት ቀየረችው" በማለት በደማቁ ፃፈበት።

በምንም የማይቀየረው የእናት ፍቅር ለልጆች ስኬትና እስከ ጫፍ ለሚዘልቅ ብርታት የማይነጥፍ ስንቅ ለመሆኑ የሚጠራጠር አይገኝም። እነሆ ከላይ የቀረበው የታላቁ ሳይንቲስት ታሪክ እስከ አሁን እውነት ነው፣ ከፊል እውነት ነው እንዲሁም ያልተፈፀመ ቢሆንም ሊሆን የማይችል አይደለም እና ሌሎች አቋሞችን እያስተናገደ ቢሆንም በማስረጃ ያረጋገጠም ሆነ ያሳመነ ወገን የለም። ባለ ታሪኩ ቶማስ ትምህርት በጀመረ 3ኛ ወር ላይ በአእምሮ ዘገምተኝነት መባረሩ፣ እናቱ ወደ ትምህርት ቤቱ ሄዳ እንደተከራከረች፣ አስራ ስድስት አመት እስኪሆነው ሁሉንም የትምህርት አይነቶች እናቱ ቤት ውስጥ አስተምራው እጅግ ከፍተኛ ውጤት በማምጣት በቀጥታ ዩኒቨርሲቲ እንደገባና ስለ ሕይወት ታሪኩ ባነሳ ቁጥር "የማይገባው የተባልኩትን ልጅ እናቴ ቀርፃና ከርክማ ሳይንቲስት አደረገችኝ" ማለቱ . . . ሁሉ በአሜሪካው ላይብረሪ ኦፍ ኮንግረስ ውስጥ በሰነድነት የተቀመጡ እውነታዎች ናቸው።

የሁላችንም እናቶች እንደዚህና ከዚህ በላቀም የሚሆኑ ናቸው። ሁኔታዎች አልመች እያሉ፣ በአንዱ ሲገጥም በሌላው እየከፈተ፣ ከወዲህ ሲሞላ ከወዲያ እየጎደለ፣ ያለሙት እንደተመኙት፣ ያሰቡት እንደ ገመቱት አልሆን እያለ እንኳ፤ የእናት ፍቅርማ ቅንጣት የማይለያይ አንድ ነው። እንደው . . . እንደ ቶማስ እናት የተሳካ ሲሆን ደግሞ በጣም ደስ ይላል።



Moral Stories.com (Motivation page) "Mother's Love for a Boy"
ሰኔ 2008 ዓ.ም. - አዲስ አበባ



## ***"በሰፈሩት ቁና . . ."***

ከከተማው በቅርብ ርቀት ላይ በምትገኝ የገጠር መንደር ውስጥ የሚኖረው ገበሬ በየቀኑ ከሚያመርተው ለጋ ቅቤ አንድ አንድ ኪሎ ወደ ከተማ እየወሰደ ለደንበኛው ባለ ዳቦ ቤት ይሸጥለታል። በዚህ አይነት ለብዙ ጊዜ ቆይተው ከእለታት በአንዱ ቀን ባለ ዳቦ ቤቱ ቅቤውን ሲመዝነው ከአንድ ኪሎ በታች ሆኖ ያገኘዋል። ሁኔታው እጅግ ያበሳጨው ባለ ዳቦ ቤት ጉዳዩን በቀጥታ ወደ ፖሊስ በመውሰድ ገበሬውን በማጭበርበርና እምነት በማጉደል ወንጀል ክስ መሰረተበት።

ገበሬው ፍርድ ቤት ቀርቦ በዳኛው ተጠየቀ :-

"ስለምን ይህንን ያልተገባ ተግባር ፈፀምክ? ልኬትህስ በምን ነበር? አብራራ?" አሉት።

ገበሬውም ሲመልስ :-
"የተከበሩ ዳኛ - እኔ በገጠር የምኖር ዘመናዊውን ትምህርት ያልቀሰምኩ ገበሬ ነኝ። ክብደት የሚለካ መሳርያም የለኝም። ነገር ግን ክብደቱን የምመጥንበት የራሴ ሚዛን አለኝ" ሲል መለሰ።

ዳኛው :-
"እሽ - ታዲያ ቅቤውን በምን እየመዘንክ ነበር አንድ ኪሎ ግራም ነው ብለህ ለደንበኛህ ስታቀርብ የኖርከው?" በማለት ጠየቁት።

ገበሬውም :-
"የተከበሩ ዳኛ! - ለተወዳጁ ባለ ዳቦ ቤት ደንበኛዬ ለረጅም ጊዜ በየቀኑ አንድ አንድ ኪሎ ትኩስ ቅቤ ስሸጥለት ኖሬአለሁ። እኔም እንደዚሁ ከተማ መጥቼ ባዶ እጄን አልመለስምና ከሱው ዳቦ ቤት ባለ አንድ ኪሎውን ሙልሙል ዳቦ ለልጆቼ ገዝቼ እገባለሁ። ወደ ቤቴ እንደተመለስኩም የመጀመሪያ ተግባሬ ያመጣሁትን ባለ አንድ ኪሎ ዳቦ በሚዛኔ አንደኛው ወገን ላይ አስቀምጥና በሁለተኛው በኩል ለጋ ቅቤየን እየዛኩ እጨምራለሁ። ከዚያም የቅቤው ክብደት ከዳቦው ክብደት ጋር በትክክል ሲመጣጠን በጥንቃቄ አንስቼ ፕላስቲክ ከረጢት ውስጥ እከትና ለባለ ዳቦ ቤቱ ደንበኛዬ አደርሳለሁ።

የተከበሩ ዳኛ! ክቡር ፍርድ ቤት ሆይ! - ከሳሼ ባለ ዳቦ ቤት እስከዛሬ ያቀረብኩለት ቅቤ ኪሎው ጎደሎ ነው ለሚል ቅሬታው፤ እኔና ቤተሰቦቼም ከኪሎ በታች የሆነ ዳቦ ስንገዛ ኖረናልና ለሆነው ሁሉ ሊጠየቅ የሚገባው እርሱ እንጂ ሌላ ማንም ሊኖር አይችልም" ሲል ጉዳዩን በጥልቀት አስረዳ።

ዳኛው የነገሩን ጭብጥና ዙሪያ ፈርጅ በማስረጃ ካረጋገጡ በኋላ ተከሳሹ ገበሬ ከክሱ በነፃ መሰናበቱን ይፋ ባደረጉበት ውሳኔአቸው፤ ታዳሚውን ጭምር የሚያነቃና የሚያስተምር ታላቅ ምክር እንዲህ ሲሉ አከሉበት :-

***"ሁላችንም በእለታዊ ኑሯችን ውስጥ ከማንኛውም ተግባራዊ እንቅስቃሴ በፊት ለሌሎች ምን አበረከትን? ከሌሎችስ ምን ተጠቀምን? ፣ የምንሰጠው አገልግሎትና የምንቀበለው ዋጋስ ተመጣጣኝ ነውን? ብለን ራሳችንን መጠየቅና በሃቅ ሚዛን መለካት ይጠበቅብናል።***

***መታመንም ሆነ አለመታመን ውሎ ሲያድር ልማድ ይሆናል። እናም አለመታመንን እንደዋዛ የተላመዱ አንዳንድ ሰዎች በቀጥታ ፊት ለፊት ይዋሻሉ። አለመታመን የጠናባቸው ብሎም ወደ ግል ባህሪነት የተቀየረባቸው ደግሞ እንደጉድ ሲዋሹና ክህደትን ሲፈጽሙ ቅንጣት የስሜት ለውጥ አይስተዋልባቸውም። እስከመጨረሻው እውነቱን ለማወቅ ካለመፈለጋቸውም በላይ ራሳቸውን ጭምር ያጭበረበሩ ቀጣፊዎች እነዚህኞቹ ናቸው።***

***ወገኖቼ - መታመን የሚጀምረው ከራስ ነው፣ ለየትኛውም አይነት ወንጀልና ሀጥያት ደግሞ መጀመሪያው እውሸት ነው። ስለዚህ በምንም አይነት አትዋሹ። ሁላችሁም የናንተ ያልሆነውን ባለመንካትና የማይገባችሁን ሁሉ ባለመውሰድ፤ ለህዝብና ለሃገር ታማኝ ሁኑ"። በማለት ምክራቸውን ደመደሙ።***

ምንጭ: የሥነ ምግባር ትምህርቶች ድረ ገጽ www.thelivingtreasure.com –
"A POUND OF BUTTER"
ሚያዝያ - 2006 (ዓ.ም.) አዲስ አበባ







## "ማንነትና ምንነት"

ከእለታት አንድ ቀን ገበሬው እርሻው ዳር ሲዘዋወር . . . ወድቆ ያገኘው የንሥር አሞራ ጎጆ፤ ውስጡ ሙቀት ያልተለየው አንድ እንቁላል ነበረበትበት። እንቁላሉን አንስቶ ወደ ቤቱ ወሰደና ዶሮው ከታቀፈቻቸው እንቁላሎች ማሃከል አስቀመጠው።

ጊዜው ሲደርስ ቅርፊቱን ፈልቅቆ የወጣው የንስር አሞራ ጫጩት፤ ከሌሎቹ የዶሮ ጫጩቶች ጋር ትላትል ፍለጋ የገበሬውን ጓሮ ሲጭር፣ ጥሬ ሲለቅምና ግቢው ውስጥ ላይ - ታች ሲል የጫጩትነት እድሜውን ገፋ። እንደ ዶሮ ይጮሃል፣ ያስካካል፣ ክንፎቹን እያርገበገበ ጥቂት እርምጃዎችን ዝቅ ብሎ ለመብረር ይሞክርና ይወርዳል፣ ሌላም ሌላም . . . እነሱ የሚያደርጉትን ሁሉ እያደረገ ራሱን ከገበሬው ዶሮዎች መሃከል እንደ አንዱ በመቁጠር አደገ።

አመታት አለፉ፣ ንሥር አሞራው እድሜ እየተጫኘው ከጉልምስና ወደ ሽምግልና ተሸጋገረ። በዚህ አይነት በመኖር ላይ ሳለ አንድ ቀን ገበሬው ግቢ ውስጥ ከዶሮ ወንድሞቹ ጋር ሆኖ መሬት ሲጭር፤ ድንገት ወደ ላይ ቀና አለና ባየው ነገር ፈዞ ቀረ። ጥርት ባለው ሰማይ ላይ በተቃራኒ አቅጣጫ በሃይል የሚነፍሰውን ነፋስ ከምንም ሳይቆጥር፤ በረጃጅም ወርቅማ ክንፎቹ እየቀረጠ በታላቅ ግርማ ሞገስ የሚበር ትልቅ አሞራ ነበር። ትንፋሹ ቁርጥ ቁርጥ እያለ አጠገቡ የነበረውን አውራ ዶሮ ጠየቀው . . . "ይሄ ደግሞ ማነው?"

"ይህ የአእዋፍ ንጉስ ንሥር አሞራ ይባላል" አለውና በአድናቆት ቀጠለ "ንሥር አሞራ አየሩን እንዳሻው እየተንሳፈፈበት እንዲኖር የተፈጠረ፤ እሱ የሰማይ ነው። እኛ ደግሞ የምድርን ገጽ በጥፍሮቻችን እያሰስን . . . በመሬት ላይ የምንኖር ዶሮዎች ነን" አለው።

ንስር አሞራው ወደ ላይ እንዳንጋጠጠ ቆየ - ቆየና . . . "**<u>አቤት . . . ንሥር አሞራ ሆኜ ተወልጄ ቢሆን ኖሮ !</u>**" አለ። ይለናል እውቁ ምሁር፣ ሰባኪና ደራሲ አንቶኒ ዲሜሎ "የወፎች ዝማሬ" በተባለው የመጽሃፉ ስብስብ ገጽ 27 ላይ። እናም ንሥር አሞራው እንደ ዶሮ ኖሮ የዶሮዎችን ሞት በመሞት ዓለምን ይሰናበታል። እንደዚህ ማሰቡም በዚህ . . . ገሃድ እውነታ ነው።

ቢሆን ኖሮ? . . . ቢሆን ኖሮ! . . . አዎን። ግን አልሆነምና አይሆንም። የሚሆነው መሆን ያለበት ብቻ ነው። ህይወት ሁላችንንም የምትመራን በዚህ ቅያስ ነው። እኛነታችን (ማንነታችን) ከተወለድን በኋላ ወደ ምድር ከመጣንባት የሰከንዶች ቅንጣት ይጀምራል እንጂ በየትኛውም የፍልስፍና ጎራ፣ በማንኛውም የአስተሳሰብ ጽንፍ . . . የዘር ሃረግ፣ የብሔር አጥር፣ የጎጥ ጥጋ ጥግ፣ የትውልድ መንደር፣ የቋንቋ መደብ፣ የታሪክ ጥራዞች፣ የመጠርያና ቅጽል ስሞች ወዘተ . . . በነበር የታነጹ ሃሳባዊ ድርሳናት የወሳኝነትን መሪ ሚና የመጎናፀፍ ብቃት የላቸውም። በአጋጣሚ ከተቸራቸውም የእክል ጠረን መሽተት የሚጀምረው ውሎ ሳያድር ነው።

ከዶሮ ጋር ገበሬው ግቢ ውስጥ ያደገው ንሥር አሞራ፤ ዶሮ ተብሎ፣ ዶሮ ነኝ ብሎ፣ እንደ ዶሮ ኖሮ ሲያበቃ የለም ከአሁን ጀምሮ ንሥር አሞራ ነህ ቢባል ሃቁ ስለሚተናነቀው አይዋጥለትም፣ ውስጡም አይስማማለትም። ነኝም ቢል ዶሮዎች ከልብ ስለማያምኑበት አይቀበሉትም። (ምናልባት ላይ ላዩን በማስመሰል ወይም በፍራቻ ከሚሆነው ውጭ ማለቴ ነው)። ማንነት ከውስጥ እንጂ ከውጭ ሲለጠፍ ያደናግራል። ለራስ ከጉራ ያለፈ ጥቅም ጠብ አይለውም። ለሌላም ከትዝብት በቀር ምናምኒት የሌለው የስብእና ጋሬጣ ነው።

እስኪ ለተጨማሪ ተግባቦት ስንኝ እንቋጥርለት . . .

**<u>"እኔ ማነኝ ?"</u>**

እንደ ዝግባ ዋርካ - ምድሩ ላይ በቅዬ
ጥላየን ዘርግቼ - ሥሬን አቆልቁዬ
ወጪ ወራጁን ሳይ - ክፉ ደጉን ስዳኝ
የትናንቱን ሳስብ - የዛሬውን ስቃኝ

የሀገር ሽማግሌ - የእድሜ ባለፀጋ
እውነቱን ከሃሰት - ከረምቱን ከበጋ
ሳስተውል የኖርኩኝ - ነቃሽ በመሆኔ
ፍርድና ጥያቄ - ቀረበልኝ ለኔ

የቤተሰቡ ግንድ - የትውልድ ሃረጉ
መነሻ መድረሻ - ሥያሜ ማእረጉ
የማንነት ነገር - ሰልፉን ባይረዳው
ምድብ አጠራሩ - ጨርሶ ባይገባው

የት እንደፈለቀ? - ከየት እንደወጣ?
ማረጋገጥ ቢሻው - ሊጠይቀኝ መጣ
እኔም አበከሬ - አውቀው ሥለነበር
ከሥር መሰረቱ - ነገርኩት በዝርዝር

አያትህ ጉምዝ ነው - ሃረር ነው እድገቱ
ታታሪ ገበሬ - ሚች ነው ለእምነቱ
ከቤንሻንጉል መጥቶ - ሀረር እያረሰ
ከቀየው ተስማምቶ - ላቅም አዳም ደረሰ

የመኮንኑን ልጅ - መአዛን ሲያገኛት
በፍቅሯ ተማርኮ - አማላጅ ላከባት
ከጎጃም ተዛውረው - የመጡት አባቷ
አሰቡት ነገሩን - መከሩ ከናቷ

የራሳቸው ታሪክ - ደግሞ ትዝ አላቸው
የልጅነት ጊዜ - የጉርምስናቸው
የመአዛን እናት - የት እንዳገኟቸው ?
ስልጠና ላይ ሳሉ - ሆለታ ነበረ - የተዋወቋቸው
ወይዘሮ ከድጃ - ያሁኗ ሚስታቸው
እናታቸው ትግራይ - አባት ሸዋ ናቸው

አባትህ ሲወለድ - የነበረው ፌሽታ
ዳንኪራው - ጪፈራው - ያያቶችህ ደስታ
ፍጹም አልረሳውም - አስታውሰዋለሁ
ሃቁን ለመዘከር - ብዙ ታዝቤአለሁ

አባትህ ተምሮ - ኮሌጅ በጠሰና
ኮንሶ ተመደበ - መምህር ሆነና
የሄደበት አገር - አድባሯ ብትወደው
የልጆቹን እናት - ከቱሼን ሰጠችው
ከቱሼ ጠይሚ - የነ ጀማሎ እናት
አባቷ ከደቡብ - እናቷ ካፋር ናት

የናትህ ማህፀን - አምላክ የባረከው
ያባትህን ግቢ - ልጅ በልጅ አረገው
ስምንት ወንድሞችህ - አንተ ዘጠነኛ
ተምሳሌተ አገር - ሆናችሁን ለኛ

ጀማል የበኩሩ - ቢሻሜን አገባ
ኤጋሲም ጎልምሶ - ከብርቂ ተጋባ
ቢሻሜና ብርቂ - እናት አባታቸው
ከሃረር ከድሬ - ከባቲና ካዲስ የበቀሉ ናቸው ።

ኢብራሂም ዝማምን - ኦኬሎ ደራርቱን
በካሎ ፋጢማን - ባሩሌ ጃሂቲን
ደቻሳ ሰሚራን - ምሩጽም ደጊቱን
አንተም አለሚቱን - አገባችሁና
ደመቀ ጎጇችሁ - ትዳራችሁ ፀና
ወልዳችሁ ሳማችሁ - ዘርታችሁ ቃማችሁ
ኑሯችሁ ሠመረ - ተባረከላችሁ
አገር ምድሩን ሞላ - በልጅ ታደላችሁ

የጥንቱ እንደዚህ ነው - ይኸው አስረዳውህ
ከወዲህ ያለውን - ሁሉንም ታውቃለህ

አንተም እንደዚያ ነህ - ሌሎችም እንደዚህ
ያልኖርከበት ነገር - ከወዴት ይምጣልህ ?

ልብ ብለህ ስማኝ - እውነቱን ልንገርህ
ከውልደትህ ጀምር - ሥንክ ሳሩን ትተህ
የቱንም ሳትሆን - አንተ ሁሉንም ነህ
ኢትዮጵያ ያንተ ነች - አንተም የኢትዮጵያ ነህ

ሁሉም አንተን ሆኖ - አንተም እንደነሱ
በጋራ ስታጭዱ - በደቦ ስታርሱ
ሃዘን መከራውን - ስትደራረሱ - ባንድ ስታለቅሱ
ሰርግና ድግሱን - ስትገባበዙ - ስትጎራረሱ
መከባበር ፀንቶ - ፍቅራችሁ አብቦ - እንዲህ ተዋዳችሁ
የመኖራችሁ ልክ - ምስጢር በረከቱ - ያስተሳሰራችሁ

ኢትዮጵያዊነት ነው - አክብሩት፣ አምልኩት፣ ጠብቁት፣ አብራችሁ
እሱ ነው መልህቁ - እሱ ነው ኪዳኑ - አልፋና ኦሜጋ - እናንተነታችሁ
አላህ አደብ ይስጥህ - እግዚያቤር ምህረቱን - አንድየም ልቦና
ቀናውን የሚያስብ - ደጉን የሚፈጽም - በቀልን ጠራርጎ . . . ፍቅርን የሚያፀና ።

> የታሪኩ ምንጭና ደራሲ - አንቶኒ ዲሜሎ - Anthony de Mello S. J.
> “THE SONG OF THE BIRD” and “AWARENESS”
> ከ "የወፎች ዝማሬ" ስብስብ ታሪኮች “ንሥር አሞራው” - "The eagle"
> ጥር - 2008 ዓ.ም. - አዲስ አበባ



## "የዘጠና በአስር (90/10) መርህ"

ዛሬ እንደ ወረደ የማወጋችሁ በህይወቴ ትልቅ ትምህርት የቀሰምኩበት ገጠመኜን ነው።

አምና የክረምት መባቻ ላይ ሥራ ውዬ ወደ ቤት ለመግባት ታክሲ እጠብቃለሁ፤ ወትሮ በራሴ መኪና ስለምጠቀም ወረፋና ግፊያው ምቾት ነስቶኛል። በመሃሉ ታክሲው መጣና ለመግባት ስንተራመስ አንድ ተሳፋሪ ረገጥከኝ ብሎ አላስፈላጊ የስድብ ናዳ አወረደብኝ። ድሮውንም ደመ ፍሉ ነኝና አፀፋውን መለስኩለት፤ ሁኔታው ተካረረና ወደ ግብግብ ብሎም ወደ ለየለት ድብድብ ተሸጋገረ። እንደ ምንም ገላግለውን የተቀዳደደና በጭቃ የተለወሰ ልብሴን ሳይ እፍረት ተሰማኝ። ኪሴን ዳበስኩ መነጽሬ ተሰባብሯል፤ የገንዘብ ቦርሳዬ የለም - ሌላ ውርደት። አንድ ሰው ስሜን ጠርቶ ከግርግሩ መሃል ጎትቶ አወጣኝ፤ አስታወስኩት . . . መምህሩ አብሮ አደግ ጓደኛዬ ተሻገር ነው። ከተያየን በትንሹ ሃያ ዓመት ያልፈናል።

"ያ ግልፍተኛነትህ አብሮህ አረጀ? በል! እንደዚህ ሆነህስ ትቼህ አልሄድም" አለኝና አጠገቤ ቆመ። ቦርሣዬ እንደጠፋ፣ ውስጡ ከነበረው ገንዘብ ይልቅ መታወቂያ፣ መንጃ ፈቃድ፣ የባንክ ካርዶችና ሌሎቹ ሰነዶች እጅግ አስፈላጊ እንደሆኑ ነገርኩት። ዙሪያ ገባውን አሰስን፣ ያገኘ እንዳለ ጠየቅን . . . የለም።

"ጊዜ ማባከን ነው፤ ከዚህ ውዝግብ የተጠቀመ ቢኖር የቦርሳው ሌባ ብቻ ነው" አለኝና ተያይዘን ወደ መኪናው አመራን። አደባባዩን እንዳለፍን ወደ ቀኝ ዞረና "እስቲ እዚህ ቡና እየጠጣን ተረጋግተህ እንጫወት" በማለት ካፌው ፊት ለፊት መኪና ውስጥ ተቀምጠን ያንን የማይረሳ ወግ ጀመረልኝ።

"በቅድሚያ ስለ መርህ - ዘጠና በአስር [THE 90/10 PRINCIPLE] ምን ያህል ታውቃለህ?" ሲል ጠየቀኝ።

ምንም - ስል መለስኩለት።

"በጥሞና ተከታተለኝ - በሚገባ አስረዳሃለሁ" በማለት ቀጠለ . . . "መርህ ዘጠና በአስር - በሚገጥሙን ሁኔታዎችና በምንሰጣቸው አፀፋዊ ምላሾች ላይ ተመስርቶ በእርግጠኝነት የእለት ተእለት ህይወታችንን ሊቀይር የሚችል ድንቅ ፍልስፍና ሲሆን የራሱ መሠረታዊ ህግጋቶች አሉት። በጥልቀት ሲተነተኑ . . . የህይወታችን 10 % (አስር በመቶ) በሚገጥሙን ነገሮች የተሞላ ሲሆን ቀሪው የህይወታችን 90 % (ዘጠና በመቶ) ደግሞ ለሚገጥሙን ነገሮች በምንሰጠው ምላሽ የሚወሰን ነው። እነኝህ 10 % የሚሆኑትና የሚያጋጥሙን ነገሮች (ሁኔታዎች) እኛ ልንቆጣጠር የማንችላቸው ናቸው።

መኪናውን ከመበላሸት ልናግደው አይቻለንም፣ አውሮፕላኑ ዘግይቶ በማረፉ ምክንያት ስለተሰናከለው እቅዳችን ምንም ማድረግ አንችልም፣ አልያም አንድ አሽከርካሪ መንገዱን በመዝጋቱ ምክንያት የተፈጠረው የትራፊክ መጨናነቅ እና የመሳሰሉት ሁኔታዎች ከኛ ቁጥጥር ውጪ የሚፈፀሙ 10 በመቶ የእለት ተእለት ገጠመኞቻችን ናቸው።

የተቀሩት 90 % ሁኔታዎች እኛ የምንፈጥራቸውና ልንቆጣጠር የምንችላቸው ሲሆኑ። እንዴት? ቢባል ለገጠሙን ሁኔታዎች (ከላይ 10 % ላልናቸው ጉዳዮች) የምንሰጣቸው አፀፋዊ ምላሾች (Reactions) ስለሆኑ ነው።

ቀዩን መብራት ልንቆጣጠረው አንችልም - ነገር ግን ለቀዩ መብራት የምንሰጠውን አፀፋዊ ምላሽ መቆጣጠር እንችላለን። ሰዎች እንዳይተነኩሱን ወይም ጥቃት እንዳያደርሱብን ማድረግ አይቻለንም፤ ምክንያቱም ውስጣዊ ስሜታቸውንና እቅዳቸውን ከቶም አናውቀውምና - ነገር ግን ትንኮሳው ወይም ጥቃቱ ከደረሰብን ወይም ካጋጠመን በኋላ የምንሰጠውን አፀፋዊ ምላሽ መቆጣጠር የኛ ፈንታ ስለሆነ ነው።

የበለጠ ግልጽ ለማድረግ **10 በ 100** ልንቆጣጠር ስለማንችላቸው (ከኛ ውጪ ስለሚፈፀሙ) ነገሮችና **90 በ 100** ልንቆጣጠር ስለምንችላቸው ወይም በኛ የሚፈፀሙ ነገሮች አንድ ምሳሌ ልጥቀስልህ። ጠዋት ሥራ ለመሄድ ቁርስህን በመብላት ላይ ነህ፣ ባለቤትህና ትንሿ ልጅህ በምግብ ጠረጴዛው ዙሪያ ተቀምጠዋል። ድንገት የልጅህ የሻይ ስኒ ከእጇ አምልጦ ቡና ማቅረቢያው ላይ ወደቀና ውስጡ የነበረው ቡና ነጩ ሸሚዝህ ላይ ተደፋ።

ልብ በል! የሆነው አንተ ልትቆጣጠር የማትችለው ክስተት ነበር፤ ነገር ግን ሆኗል። ቀጣዩ ሁኔታ የሚወሰነው አንተ ለድርጊቱ ምን ምላሽ ሰጠህ? በሚለው ነው።ዘለህ ተነሳህ፣ ትንሿ ልጅህ ላይ የእርግማን መአት ታወርድ ጀመር፣ በቁጣና በስድብ አዋከብካት፣ በመቀጠል ወደ ሚስትህ ዞርክ፣ እንደ መብረቅ ጮህክባት፣ የቡና ማቅረብያውን ጠረጴዛው ዳር ላይ ባታስቀምጪ ኖሮ ይህ አይሆንም ነበር ስትል ኮነንካት፣ አላስፈላጊ አተካራ ገጠማችሁ . . .። ወደ መኝታ ቤት ሄደህ ሸሚዝህን ቀይረህ ስትመለስ ልጅህ በለቅሶ እየተነፋረቀች ቁርሷን ለመጨረስ ትታገላለች፣ እየተንጎራደድክ ጠበቅሃት፣ ባለቤትህ ስለረፈደባት ወጥታለች፣ ሰአትህን አየህ ረፍዷል፣ ልጅህ ሰርቪሱ አምልጧታል፣ ስለዚህ እሷን ትምህርት ቤት ማድረስ አለብህ . . . በፍርሃት የተረበሸች ልጅህን እያቻኮልክ መኪናህ ውስጥ ገባህና በፍጥነት ማሽከርከር ጀመርክ። በሰዓት 60 ኪ. ሜትር የፍጥነት ገደብ በተወሰነበት መንገድ ላይ በሰዓት 80 ኪ. ሜ. በማሽከርከርህ የትራፊክ ፖሊስ አስቆመህና የቅጣት ወረቀት እስኪቆረጥልህ ሌላ 10 ደቂቃዎችና 180 ብር አባክነህ ደረስክ። ልጅህ "ደህና ዋል ባባ" ሳትልህ ወደ ክፍሏ ሮጠች። ቢሮ ስትገባ ግማሽ ሰዓት አርፍደሃል፣ የሚያሳዝነው ደግሞ የስራ ማስታዎሻዎችና ላፕ ቶፕህ ያለበትን ቦርሳ ረስተሃል። አይጣል ነው! ከጅምሩ ቀንህ ተረበሸ፣ ማታ ወደ ቤት ስትገባ ደግሞ ያስቀየምካቸው ቤተሰቦችህ ጉዳይ ጥቂት ዋጋ ያስከፍልሃል።

ለምን? - ሲጀመር ጠዋት ላጋጠመህ ነገር በፈፀምከው አፀፋዊ መላሽ ምክንያት።

ለተረበሸው ቀንህ መንስኤው ምንድነው?
ሀ/ የፈሰሰው ቡና? ለ/ ትንሿ ልጅህ? ሐ/ ትራፊክ ፖሊሱ? መ/ አንተ።
መልሱ ፡- መ/ አንተ። የሚለው ነው።

ከአንተ ቁጥጥር ውጭ ስለፈሰሰው ቡና ምንም ማድረግ አትችልም። በ 5 ሰከንድ ውስጥ የወሰድከው ምላሽ ግን ሙሉ ቀንህን አመሳቅሎብሃል። ይህ ነው እንግዲህ ልታደርገው ስትችል ሳታደርገው የቀረኸው (ልትቆጣጠረው ስትችል ሳትቆጣጠረው የቀረኸው)። ቡና ፈሰሰብህ፤ ልጅህ ደነገጠች፣ ካንተ የሚጠበቀው የኔ ማር ሌላ ጊዜ የሻይ ስኒሽን በጥንቃቄ ያዢ ብለህ፣ ሸሚዝህን ቀይረህ፣ ቦርሳህን ይዘህ፣ ሚስትህ በመልካም ምኞት ተሰናብታህ፣ ልጅህ እጇን አውለብልባልህ አውቶብሷ ውስጥ ስትገባ አይተሀት . . . ከመግቢያ ሰአትህ 20 ደቂቃ ቀድመህ ቢሮ ስትደርስ - ፈገግታና ብሩህ ፀዳል የተላበሰ ገጽታህን ብቻ የተመለከቱ ባልደረቦችህና አለቃህ፤ ውሎህ ምን ያህል ባማረ ሁኔታ እንደጀመረ ይገነዘቡ ነበር።

ልዩነቱን አስተውል! - ሁለት የተለያዩ ታሪኮች። መነሻቸው አንድ ሆኖ መጨረሻቸው እጅግ የተለያየ ሆነ። ለምን? ለነገሮች በሰጠሃቸው የተለያዩ አፀፋዊ ምላሾች ምክንያት ነው። እንግዲህ - ከቁጥጥራችን ውጪ ስለሚገጥሙን 10 % ነገሮችና ልንቆጣጠር ስለምንችላቸው 90 % ምላሾች ይህን ያህል ከተረዳህ መርህ 90/10 ን ለመተግበር የሚረዱ ጥቂት ነጥቦችን ላክልልህ።" አለኝና ምን ያህል እንደተረዳሁትና እየተከታተልኩት እንደሆነ ለመረዳት ቆም አድርጎ አየኝ፣ እኔም መመሰጤን በምልክት ገለጽኩለት፣ እሱም ማብራራቱን ቀጠለ።

አንድ ሰው ተነኮሰህ (ፀያፍ ወይም የማይገባ ቃል ተናገረህ እንበል) እንደ ስፖንጅ ምጥጥ አድርገኸው ተቀመጥ አልልህም፤ ያልተመዘኑ ትችቶችና ፀያፍ ንግግሮች ምን ያህል እንደሚያሳምሙን ስለማውቅ ትቶ ለማለፍ ፈተናው ከባድ ነው። ነገር ግን አፀፋዊ ምላሽህ - የረጋ፣ የሚያስከትለውን ውጤት ያገናዘበ፣ ከሰዳቢህ የተሻልክና የሰከነ ባህሪ ባለቤት መሆንህን የሚገልጽ ከሆነ ተናጋሪህ ያፍራል፤ ውሎህም በሰላም ያልፋል። በሃይለ ቃል የታጀበ፣ በቁጣና ደም ፍላት የሚወረወር መልስ የተሳሳተ አፀፋዊ የጥፋት ምላሽ ስለሚሆን - ከወዳጅ ጓደኛ ያቃቅራል፣ ያሳፍራል፣ ያሸማቅቃል፣ ለብስጭትና ጭንቀት ይዳርጋል፤ አልፎ ተርፎ ለከፋ የኑሮ ምስቅልቅልና . . . ወዘተ ውጤቶች ይዳርጋል። ይህንን በሌላ ተጨማሪ ምሳሌዎች ላብራራልህ።

ባልተገባ ሁኔታ እየከነፈ መጥቶ መንገድ ለዘጋብህ አሽከርካሪ አፀፋዊ ምላሽህ ምንድንነው? ትዕግስትህ ከቁጥጥር ውጪ ይሆናል? መሪህን እየደበደብክ ትጮሃለህ? አንገትህን በመስኮቱ አስግገህ የስድብና የእርግማን ቃላት ታወርዳለህ? የደም ግፊትህ እስኪያሻቅብ በንዴት ትንዘፈዘፋለህ?፣ ልትደባደብ ዘለህ ትወርዳለህ? ወይስ . . . ሌላ ሌላ። ልብ በል! ካሰብከበት ለመድረስ 10 ሰከንዶች ብትዘገይ ማን ይጨንቀው ይመስልሃል? ባንተ ጥፋትስ ከጀርባህ ላሉ መኪኖች ሁሉ ለምን ጦስ ትሆናለህ? . . . <u>ምን ጊዜም የ 90 በ 10ን መርህ አስታውስ እናም እንደ ዋዛ እለፈው።</u>

የመብራት ወይም የውሃ በለው የስልክ ሂሳብ ለመክፈል ረጅም ሰልፍ ተሰልፈሃል፤ ክፍያ ግን አልተጀመረም፤ ከስራ የተፈቀደልህ ሰዓት አጭር ነው። ምክንያቱን ትጠይቃለህ የጥበቃ ሰራተኛው "መብራት ተቋርጧል እንደመጣ ይጀመራል" ሲል ይመልስልሃል። ትጠብቃለህ . . . ትቆያለህ - ትቆያለህ አልተጀመረም። ቁጣህ መቀጣጠል ይጀምራል፣ ቃላቶችህ ከማጉረምረም ወደ ጩኸት ከፍ ይላሉ፣ በመብራቱ መሄድና መምጣት ውስጥ ምንም የማይመለከተው የጥበቃ ሰራተኛ ላይ ብሶትህን ትዘረግፋለህ፣ ዘለፋና እርግማንህ ጣራ ይነካል፣ በንዴት ትወራጫለህ . . . . ለምን?። ለምን ሰከን ብለህ በጊዜህ አትማርም? ሌሎቹ ሰልፈኞች ስለምን ዝም አሉ? ብለህ አዟረህ አታስተውልም?። እንደዚህ ስልህ በደልና መገፋት ሲደርስብህ፣ የተዛባ ፍትህና መድሎ ሲያጋጥምህ በዝምታ እለፈው ማለቴ አይደለም። ምላሽህ የተጠና፣ በተገቢው ሁኔታ ለትክክለኛው ክፍል የሚቀርብና ውጤታማነቱም የሚያስተማምን እንጂ በጊዚያዊ ብስጭትና ቁጣ የሚነሳ እንዳይሆን ተቆጣጠረው ማለቴ ነው።

አሁን መርህ 90/10 ን ተገንዝበሃል! ሞክረው የሚቀነስብህ ነገር የለም። የዘጠና በአስር መርህ እጅግ ድንቅና ተአምረኛ የህይወት መመሪያ ነው። የሚያውቁና የሚጠቀሙበት ግን እጅግ በጣም ጥቂት ናቸው። በመሆኑም በሚሊዮን የሚቆጠሩ ህዝቦች ለማያገግም ጭንቀት፣ ለውስብስብ ችግሮችና ለከፋ የኑሮ ፈተና ሲዳረጉ እንደ ልብ፣ ኅብለ ሰረሰርና አእምሮ . . . በመሳሰሉ ህመሞች የመጋለጥና የመጠቃት አደጋ አጋጥሟቸዋል። ሁላችንም መርህ 90 በ 10 ን ማወቅና ተግባራዊ ማድረግ ይገባናል - በእርግጠኝነት የእለት ተእለት ህይወታችን ይቀየራል!።"

በማለት ታሪኩን አጠቃለለልኝ። በእኔ በኩል የህይወት መመሪያየ አድርጌዋለሁ እስቲ እናንተም ሞክሩት።



ምንጭ ፡- THE 90/10 PRINCIPLE –
ደራሲ ፡- ዶክተር ስቴቨን ኮቪይ (Dr. Stephen Covey)
ሰኔ ወር 2006 ዓ.ም. *** አዲስ አበባ



## "ጽናት"

ጃፓናዊው የጁዶ መምህርና ማስተር (በጃፓንኛ ሴንሴ) እድሜ ዘመናቸውን በፈጁበት የጁዶ ስፖርት ጥበብ አንቱ የተባሉና በመጀመርያው መስመር ላይ የተቀመጡ አሰልጣኝ ናቸው። ዛሬ በገጠማቸው ሁኔታ ግን እጅጉን ተገርመዋል። ነገሩ ወዲህ ነው . . . ።

ገና በማለዳ እለታዊ ሥራቸውን እንደጀመሩ፤ ጥቅጥቅ ካለ ሰውነት ጋር ንቃትና ቅልጥፍና የሚነበብበት ወጣት ልጅ ሰተት ብሎ ወደ ክፍላቸው ገባ። አንጋፋው ማስተር ያለ ግራ እጅ ተወልዶ ይህንን ዓለም በአንድ እጅ ብቻ የተቀላቀለውን ወጣት፤ በጉድለቱ ምክንያት አስቸጋሪውን የጁዶ ስልጠና እንደማይቋቋም በማሰብ የሚመልስ ወኔ አልነበራቸውም። ይልቁኑ ጠጋ ብለው አዩት የቀኝ እጁን ፈርጣማ ጡንቻ፣ የቀልማማ እግሮቹን ጥንካሬና ከእድሜው የገዘፈ ትከሻውን ሲያስተውሉ አእምሯቸው አንድ ፍንጭ ፈነጠቀላቸው። ጥቂት መጠይቆችንና ሙከራዎችን ካደረጉለት በኋላ በዳበረ የአካልና የመንፈስ ጥንካሬው በመደነቅ ቅንጣቷ ብልጭታ ነብስ ዘርታ ወደ ስኬት ስትቀየር ታየቻቸው፤ እናም ፈገግ አሉ . . . ያኔ ብቃቱን አመኑለት። ስልጠናውንም ጀመረ።

ይህ ወጣት ከህፃንነቱ ጀምሮ በጁዶ አሸናፊ መሆን የሌት ተቀን ህልሙ ነበር። ዳገት ቁልቁለቱን በመሮጥና ሳያሰልስ በመልፋት ራሱን ለእስፖርቱ ሲያዘጋጅ ኖርዋል። በአንድ እጁ ምንም እንደማይሆንለትና አርፎ እንዲቀመጥ ከቅርብ ቤተሰቦቹ እስከ ሩቅ የመንደሩ ሰዎች፤ እንደ ምክር በዞርታ፤ እንደ ቁጣም በቀጥታ ነግረውታል። እሱ ግን ወይ ፍንክች አልተበገረም። በጥረቱ እንደገፋ ቀኑ ደርሶ ዛሬ ወደ ማስተሩ መጣ፣ አላሳፈሩትም ከሚወደው የጁዶ እስፖርት ጋር እንዳይላቀቅ አድርገው አቀራኙት።

ሽማግሌው የጁዶ መምህር የመጀመርያውን ስልት አሳዩትና ደጋግሞ እንዲያጠናው ነገሩት። ልጁም ፍጹም በሆነ ፍላጎት ሲተገብረው ቆየ። በሁለተኛውም ሳምንት ያንኑ ተመሳሳይ የጁዶ እንቅስቃሴ እንዲለማመድ አዘዙት። በሦስተኛውም - በአራተኛውም . . . እያለ በቀጣዮቹ ተከታታይ ሳምንታትም ቀጠለ። እሱ መጀመርያ የተማረውን አንድ አይነት እንቅስቃሴ በየእለቱ እየደጋገመ ሲሰራ ሌሎቹ ተማሪዎች ግን በየጊዜው የተለያዩ ቴክኒኮችን እንዲማሩ መደረጋቸውን አየ። ይሁን እንጂ ምክንያቱ ባይገባውም በራሱ በኩል መስራቱን ሳያቋርጥ በርካታ ወራት አለፉ።

አንድ ቀን ወደ አሰልጣኙ ሄደና በትህትና . . . "ሴንሴ" ብሎ ጠራቸው (ያው ከወገቡ እጥፍ ብሎ እጅ እየነሳቸው መሆኑን በዓይነ ኅሊናችሁ እንደምታዩ እየገመትኩ) "አቤት" አሉት "እስካሁን የተማርኩት አንድ አይነት ያጁዶ እንቅስቃሴ ብቻ ነው። ሌሎች ስልቶችን አልማርም እንዴ?" በማለት ጠየቃቸው።

ሴንሴም መለሱለት! "ትኩረትህን ሁሉ በዚህ ስልት ላይ አድርግ። ይህ ልዩ እንቅስቃሴ ልታጠናው የሚገባህና ምንግዜም የሚያስፈልግህ በመሆኑ ለአንተ ወሳኝ ስልት ነው" አሉት። ልጁ በታዘዘው መሰረት በብቸኛው ስልት ላይ አተኩሮ እለታዊ ልምምዱን ያለመታከት በመስራት የሴንሴን መመርያ ቅንጣት ሳያስተጓጉል ቀጠለ።

ከዚያ በኋላ አመታት ተቆጠሩና ባለ አንድ እጁ ወጣት የጁዶ ተማሪ የመጀመርያ ብሄራዊ ውድድሩን የሚያደርግበት ቀን ደረሰ። አብሮት የተወለደ ያህል የሚሰማው - ጁዶ፣ የረጅም ጊዜ ህልሙ - ጁዶ በሕይወቱ ውስጥ ወደ አንድ ምእራፍ የሚሸጋገርበት ልዩ እለት . . . መጣ። የመወዳደርያ ነጭ ካፖርቱን ለብሶና ጥቁር መቀነቱን ሸብ አድርጎ፣ ሴንሴ ከፊት ከፊቱ ሆነው እየመሩት ወደ ፍልሚያው ሜዳ ገባ። በግራና በቀኝ በኩል የተሰለፉትን ባለ ብዙ ልምድና ታዋቂ ተወዳዳሪዎች ሲመለከት ድንጋጤና ደስታ እኩል ውርር አደረጉት። ሌሎቹ እስፖርተኞችም ሆኑ ዙርያውን ችምችም ያሉት ተመልካቾች ከአድናቆቱ አላመለጡም። ልጅነቱና በተለይ የመጀመርያው ባለ አንድ እጅ ተወዳዳሪ መሆኑ እንግዳ ነገር ሆኖባቸው፣ ሁሉም በግርምት እንዳፈጠጡ ውድድሩ ተጀመረ። ሌላ ድንቅ ነገር . . . ታዳሚው ባልጠበቀው ፍጥነትና ዘዴ የመጀመርያውን ግጥሚያ አዲሱ ልጅ አሸነፈ። በዚህ አላበቃም ከዳር እዳር የሚናኘው ወሬ ሳይቀዘቅዝ፣ በቀናት ውስጥ ሁለተኛውንም ግጥሚያ በቀላሉ ረታና ባልገመታቸው ድሎች ሲደሰት ከረመ።

ሦስተኛው ውድድር ግን ከፊተኞቹ ግጥሚያዎች ጠንከር ያለ ነበር። በተፋፋመው ትግል መሃል ያችን አንድያ ስልት ተጠቀመና አሸናፊነቱን ተቀዳጀ። ለረጅም ጊዜ በኖረውና አሁንም በሚሰራበት የውድድር መመርያ እንደሚታወቀው፣ ትንሹ ልጅ በሚሳተፍበት የውድድር እርከን የሦስተኛው ግጥሚያ ቀጥታ ባለድል ወደ ፍፃሜው ለማለፍ አራተኛውን ውድድር ማሸነፍ ግድ ስለሚለው ቀጣዩ ዝግጅት እጅግ ወሳኝ ነበር። በእለቱ ከታላቅ የአሸናፊነት ወኔ ጋር ወደ ሜዳ የገባው ልጅ በለመደው እንቅስቃሴ ተጋጣሚውን ዘረረና ከፊት ለፊቱ የሚጠብቀው ዋናውና የመጨረሻው መሆኑ ተረጋገጠ። ከወዲሁ ባለው ጊዜ እሱ ፍጹም ላልገመተው ከባድ ውድድር ሲዘጋጅ በሌላ በኩል የዜና ማሰራጫዎች ግንባር ቀደም ዘገባና ወሬ ሁሉ ይኸው ታላቅ ውድድር ሆኖ ሰነበተ።

እንዲያ - እንዲያ ሲል . . . አይደርስ የለም የዋንጫው ቀን ደረሰ ። በተመልካች ጥቅጥቅ ያለው ስታድዮም በሆታና በዜማ እንደ ደመቀ በናፍቆት የሚጠበቁት ሁለቱ ተፋላሚዎች ከአሰልጣኝ (ሴንሴዎቻቸው) ጋር ሆነው ወደ ሜዳው ገቡ። ትግሉ ተጀመረ! . . . አንዴ ከፍ አንዴ ዝቅ በማለት ይካሄድ የነበረው የሁለቱ ተፋላሚዎች ብርቱ ትንቅንቅ በመጨረሻዎቹ ዙሮች ሚዛኑ ወደ አንድ ጎን አጋደለና ባለ አንድ እጁ እስፖርተኛ ተጠቃ። በዚህ ሳያበቃ ጉዳት እንደ ደረሰበት የገመቱት ዳኛ አጭር የእረፍት ጊዜ ሰጡ። ከእረፍት በኋላ በተመሳሳይ ሁኔታ የቀጠለውን ጨዋታ ዳኛው በድንገት አስቆሙና አዲሱ ልጅ በበቃኝ እንዲወጣ ጠየቁት። አስደንጋጭ ውሳኔ

ነበር። ሴንሴው ተቃወሙ፣ የልጁ ጥንካሬና ብቃት እንዳልተዳከመ በመግለጽ ትግሉ እንዲቀጥል ያቀረቡት ጥያቄ በመጨረሻ ማስጠንቀቅያ ተቀባይነት አገኘና ውድድሩ ቀጠለ። ትግሉ ይበልጥ ተጧጧፈ . . . ቅንጣት ስህተት ለከፋ አደጋ ትዳርጋለች፣ ጥንቃቄ በተሞላበት ስልት የሚደረገው ስንዘራና መከላከል፣ ጠለፋና ትንቅንቅ እጅግ ፈታኝ ነበር። በዚህ ወሳኝ ቅጽበት የልጁ ተቃራኒ ታጋይ ግራ ክንዱን ከመከላከያ ዞን በማውረድ ያልተጠበቀ ስህተት ፈፀመ። ትንሹ ልጅ ግን ክፍተቷን ተጠቀመባት። ወሳኝዋን ስልት በተፈላጊዋ ሰከንድ ሥራ ላይ አዋላት . . . ተአምረኛዋን ምት ሰነዘረ፤ እንደ እንዝርት በሚሾር ፍጥነት ከግራ ወደቀኝ ተሽከርክሮ በጠንካራው እግሩ የወሰደው እርምጃ ተፋላሚውን በአየር ላይ አንሳፎ ከመሬት ደባለቀው። በዚያው እጅግ ድንቅ ሊባል በሚችል ሁኔታ ባለ አንድ እጁ የጁዶ ስፖርት ተወዳዳሪ አሸነፈ !።

ትንሹ ልጅ ያጠናትን አንድና አንድ ስልታዊ እንቅስቃሴ ተጠቅሞ ግጥሚያዎቹን በድል እንደተወጣ ሁሉ፤ ዛሬም ግዙፉንና ታዋቂውን የጁዶ አትሌት በለመደው ዘዴ ገረሰሰ። በኩራት ወደ ፊት ተራምዶ በአንድ እጁ የሻምፒዮናዊነቱን ዋንጫ አነሳ . . . እውነትም ይህ ተአምር ነበር - ተአምር።

ሁሉም ነገር ተጠናቀቀና በነጋታው፣ ሴንሴ ከባለ ድሉ ተማሪያቸው ጋር ሆነው ወደ መንደራቸው ለመመለስ ባቡር ተሳፈሩ። እግረ መንገዳቸውን ጥቂት ሰአት የሚወስደውን የባቡር - ጉዞ ስለውድድሮቹ ጠቅላላ ሁኔታ በመወያየትና በመገምገም ሊጠቀሙበት ስለፈለጉ፤ ጎን ለጎን ተቀምጠው ማስታወሻዎቻቸውን አወጡ። ከዚያም በእያንዳንዱ ግጥሚያ ውስጥ የተደረጉትን ነጠላ እንቅስቃሴዎች ቁጥር ሰጥተው በቅደም ተከተል ይከልሷቸው ጀመር . . . ። ልጁ በራሱ ውጤት እጅግ በመገረም . . . "በጣም አስደናቂ ሥራ ነው! በተጠና አንድ ስልት ብቻ ሙሉ ውድድሮችን እንዴት ማሸነፍ ይቻላል? ይህንን የማይታመን ብቃትና ውብ ስኬት እንደምን ሊያላብሱኝ ቻሉ?" በማለት ጠየቃቸው።

ሴንሴም - "አሸናፊነትህ ሁለት አብይ ምስጢራት አሉት። አንደኛው አንተ ለብዙ ወራት የተለማመድከውና ፍጹም የበቃህበት ስልት ከጠቅላላው የጁዶ ትምህርት ውስጥ እጅግ ከባዱና ፈታኙ ስልጠና ነበር። ሁለተኛው ደግሞ በአንተ ትምህርት ውስጥ ሰፊ ትኩረት የተሰጠው የግራ ጎንህን በፍጹም ቅልጥፍናና ጥንካሬ የመከላከል ልዩ ስልት ሲሆን በማይጠበቀው የግራ ክርንህ አቅጣጫ ተሽከርክረህ የምትወነጭፈው አስደንጋጭና ድንገተኛ ስንዘራ ከቦንብ የሚቆጠር ነው። እውነት እልሃለሁ . . . ይህንን ማንም መቋቋም አይችልም - ኮርቼብሃለሁ" አሉት።

ልጁ በደስታ ዘሎ ተነሳ፣ አንገታቸው ስር ተወሽቆ ስቅ - ስቅ ብሎ አለቀሰ የደስታ እንባ . . . በሲቃ የታጀበ ድል፣ የሚስረቀረቅ ዛግ ያሳመረው ልዩ እንባ . . . የአሸናፊዎችን ትኩስ እንባ አነባ። ሴንሴ እንደ ህፃን ልጅ አናቱን እያሻሹ አባበሉት . . . በትዝታ ወደኋላ ነጉዱ፣ በመጀመርያዋ ቀን - ለመጀመርያ ጊዜ ሲያዩት የተሰማቸው ጥልቅ ስሜትና ከእንከኑ ውስጥ ፈልፍለው ያፈኩት ስኬት . . . ሊፈስ የደረሰ እንባቸውን ዋጥ አደረጉት።

የዚህ አይነት ድል ቢያስለቅስ ሲያንስበት ነው። ወዳጆቼ እስቲ በልጁ ውስጥ ያለውን ጽናትና ጥንካሬ እዩልኝ፣ ከዚያም የመምህሩ ወደር የለሽ ብቃትና በተጠና እቅድ ውስጥ በስሎና ዳብሮ እንከን የለሽ ውጤት ያስመዘገቡበትን ሂደት መዝኑልኝ። እውነቱን ለመናገር ከላይ የጠቀስኩትን ያህል እንኳን ውስብስብ አይደለም። ያለጥርጥር የማይዋዥቅ አላማና ቀናነት ብቻ የሚፈጽሙት እጹብ ድንቅ ተግባር ነው። ልጁ የረጅም ጊዜ ህልሙን እውን ለማድረግ ጉድለቱን ከቁብ ሳይጽፈው ፍጹም ጥንካሬውን ብቻ ይዞ ወደ ጁዶ ማሰልጠኛው መጣ። ሴንሴ አዩት . . . በደንብ አዩት፤ በዚያች ቅጽበት የአእምሯቸውን የካበተ የጥበብ ጓዳ ፈተሹት፤ መልሱ ሲከሰትላቸው ፈገግ አሉ። አዎ የልጁን ደካማ ጎን ወደ ትልቅ ብቃት መቀየር፣ ከአይነኬው ግዙፍ ጉድለት ተአምራዊ የሆነ ስኬት መምዘዝ። ይህ ነው ሴንሴ አምጠው የወለዱት ትንፋሽ የሚሰርቅ ስልት። እሱ ነው በገሃድ የታየው፣ በጁዶ ስፖርት መፋለምያ መድረክ ላይ መቶ ሺህዎች ከበው ያጨበጨቡለት እውነት። የሚያሳፍርና የሚያሸማቅቅ የሚመስል ጉዳተኝነት በደስታ ጮቤ ወደሚያስረግጥና ከዳር እዳር ወደሚያበራ ድል የተለወጠበት የመጨረሻ ድንቅ እውነት፣ አሸናፊነት።

ይህንን ታሪክ እስቲ ከራሳችንና በዙሪያችን ካሉ ነገሮች አንፃር እንየው። ሁሉም በእለት ተእለት ህይወታችን ውስጥ አብረውን እየኖሩ ልብ የማንላቸው ነገሮች ናቸው። በእያንዳንዱ እንቅስቃሴአችን ውስጥ መጉደላቸው ሳይታወቀን የጎደሉ፣ አስፈላጊነታቸውን ሳንረዳ ቀርተን ያልያዝናቸው አልያም ሳናውቃቸው እንደቀረን የተረሱ ነገሮች . . .።

እኛ የረባ ህልም የለንም፣ ጥንካሬና ጽናት ይጎድለናል ወይም እናስመስላለን እንጂ ራሳችንን አንሆንም፤ ስለዚህ መጀመርያውኑ መሄድ ወደሚገባን ማሰልጠኛ አንሄድም፣ የምንፈልገውንም አናገኝም፣ የምንመኘውን ቀርቶ የጠላነውን እንኳን ማግኘት ከሰማይ ምን ያህል እንደሚርቅ ለእናንተ መንገር አያስፈልገኝም። መምህራኖቻችን ደግሞ የሚያስተምሩንን አያውቁትም፣ እቅድና ንድፉን የሚያዘጋጁላቸው ሰዎችም ከእጅ የማይሻል ምንትስ ስለሆኑ በወጉ ያልተሰናዳውን ትምህርት የምንተዋወቀው እኩል ነው። የኛዎቹ ሴንሴዎች የሚያስተምሩን ለኛ የሚያስፈልገውን ሳይሆን እነሱ የሚፈልጉትን ነው። አሰልጣኞቻችን የሚያሳዩን የማናውቀውን ሳይሆን የምናውቀውን ገልብጠው፣ የሆነውን ቀይረው፣ የሌለ አክለው ወይም የነበረውን አጉድለው ስለሆነ ልንጨምር ሄደን ግራ ገብ ሆነን እንመለሳለን። ትላልቆቹ ድክመቶቻችንን ወደ ዋና ዋና ጥንካሬዎችና ብቃቶች መቀየር ! . . . ይህ ቅዱስ ራእይ እኛ ዘንድ የማይዘገን ጉም ነው፣ እንዳማረን ይቀራል። ይልቁንስ ጥቃቅኖቹ ህፀፆቻችን ፋፍተውና ጎልብተው እንድናፍር እንድንሸማቀቅና እርስ በእርስ እንድንነካከስባቸው በገፍ ይታደሉናል። በድክመታችን መዘላለፍን፣ በጉድለታችን መተማማትን፣ በስንፍናችን መመፃደቅን፣ በሥራ ሳይሆን በወሬ ሙብለጥን ተለማምደን በተለይ በተለይ ቅጭም እንዳሉ በአደባባይ መዋሸትን
ተክነንበት ስለምንወጣ አሰልጣኞቻችንን የምናስንቅ ምልምሎች ሆነን ቁጭ ነው። እኛ ዘንድ ሴንሴም የሉ፣ ባለ አንድ እጁ ልጅም የለ፣ ለመሆንም አንሞክር፣ መሞከርያው ሜዳም ሆነ የሚያስሞክር ታጋሽ የለ . . . እንደው ምን ይሻላል? ነገሩ ባዶና ባእድ ሆነኮ።

ምንጭ ፡ from Shawn Callahan Collections: author of "Putting Stories to Work"
Title "The One armed Champion"

ጥር 2009 * አዲስ አበባ

("ሌሊቱ እርጉዝ - ፈረሴም እርጉዝ" የሚለውን ተረት አባቴ ከነገሩኝ 40 ዓመት ገደማ ይሆነዋል ፡፡)

በድሮ ጊዜ ነው አሉ። አንድ ሃገሩን አፍቃሪ ለንጉሱ ታማኝ የሆነ፣ የጠላት ጦር የሚርበደበድለት፣ ወገኖቹ የሚመኩበት ጀግና ሰው ነበር። በየዘመተበት ጦር ግንባር ከፊት ቀድሞ ተዋግቶ በማዋጋት፣ ድል በድል እየተቀዳጀ ጦሩን አስከትሎ ምርኮኞቹን እየነዳ ይመለሳል። ህዝቡ በታላቅ ኩራት እየፎከረና እየሸለለ ይቀበለውና፤ያገር ሽማግሌዎች ይመርቁታል፤ ንጉስ ደግሞ ይሾሙታል - ይሸልሙታል። እንዲህ እንዲህ እያለ . . . በማዕረግ እያደገና ስሙ እየገዘፈ፣ እሱ የሚመራው ጦርና የጦር አበጋዞቹ ዝናም እየገነነ መጣ።

ይህ ሁኔታ ያላማራቸው በንጉሱ ዙርያ የተሰባሰቡ ባለስልጣናት፣ በቅናት ተነሳስተው ተንኮል ይሸርቡበት ገቡ። ጭራሽ ያላሰበውን የሃሰት ታሪክ በመፍጠር፣ "እጅግ ጠንካራ ጦር ያለኝና በከፍተኛው የማእረግ ደረጃ ላይ የምገኝ እኔ ስለሆንኩ ንጉሱን ማውረድ አያቅተኝም" እያለ ነው የሚል ወሬ አናፈሱ። ወሬውን ያላመኑት ንጉስ፣ ነገሩን ሳይቀበሉ ብዙ ጊዜ ቢቆዩም ድግግሞሹ እየበዛ፣ ከተለያዩ ባለስልጣኖች አንደበት እየሰሙት ሲሄድ ጥርጣሬ ገባቸው። በመጨረሻም አመኑበትና ሊያጠፉት ወሰኑ። ጀግናው አርበኛ ታስሮ ለፍርድ ቀረበ።

የፍትህ ሂደቱን በተገቢው መንገድ ለማስኬድ ከወሬ ባለፈ የሚጠቀስ ተጨባጭ ማስረጃ አለመኖሩን የሚያውቁት ሹማምንት፤ ንጉሱ ዕለቱኑ አስደንጋጭ ውሳኔ አሳልፈው፣ በቀጣዩ ቀን እንዲፈፀም አመቻችተው ነበር።

በዚህ አይነት የፍጥኝ ታስሮ ለፍርድ የቀረበው ጀግና፤ የሚከተለው የንጉሱ ውሳኔ ተነበበለት ፡-

**ውሳኔ**

"ንጉሳችን አስበው፣ አውጥተው፣ አውርደው እስከ ነገ ጠዋት አንድ ሰዓት ድረስ ሁለት ጭንቅላት ያለው ፈረስ እንድታመጣ አዘዋል። ይህንን ካላደረክ ግን ልክ ከጠዋቱ ሁለት ሰዓት ላይ በስቅላት እንድትሞት የፍርድ ውሳኔ አስተላልፈዋል!" ንጉሳችን ለዘላለም ይኑሩ !!!

አቀርቅሮ መሬት መሬቱን እያየ ውሳኔውን ያዳመጠው ጀግና፣ ምንም ሳይመልስ ቆየ። ጠላቶቹ ነግቶላቸው ተሰቅሎ እስኪያዩት እየጓጉ በደስታ ሲያውካኩ፣ ወዳጆቹ ማቅ ለብሰው ሃዘን ባኮማተረው ስሜት ያነቡ ነበር ።

ጉሮሮውን ጠራርጎ መናገር ሲጀምር ሁሉም ፀጥ እረጭ አለ።

"ወገኖቼ! የውለታዬ ምላሽ ይህ ነውን? አንዲት ነገር ብቻ እናገራለሁ። ይኸውም፤ ሌሊቱ እርጉዝ ነው - ፈረሴም እርጉዝ ናት። ሃገሬ ለዘላለም ትኑር!" ብሎ ዝም አለ። በወታደሮች ታጅቦ ወደ እስር ቤት ያመራው ጀግና፤ ጠባቧ ክፍሉ ውስጥ ገብቶ ከደጅ ተቆለፈበት።

ሰከንዶች - ደቂቃዎች - ሰዓታት እየበረሩ እየተባረሩ ፤ ጠዋት ወደ ቀትር ፣ ቀትር ወደ ከሰዓት ፣ ከሰዓት ወደ ረፋድ፣ ረፋድ ወደ ምሽት፣ ምሽት ወደ ማታ፣ ማታ ወደ እኩለ ሌሊት. . . እያለፉ እየተላለፉ፣ እየተሻገሩ እየተሸጋገሩ ሄዱ ነጎዱ።

ጎህ ሲቀድ፣ ሰማዩ የአህያ ሆድ ሲመስል፣ ጀግናው እንጨት ላይ ሊሰቀል ጥቂት ሰአት ብቻ ሲቀረው፣ የጡሩንባ ድምጽ አካባቢውን አናጋ!" ጡ ጡ ጡ . . . ንጉስ አርፈዋል! ንጉስ አርፈዋል! ሃዘን ታውጇል! የቀብራቸው ሥነ ሥርዓት በቅርቡ ይገለፃል! ጡ ጡ ጡ . . ." ቀጠለ ተቀጣጠለ።

የጀግናው ሚስት ወደ እስር ቤቱ ትሮጣለች፣ ከጀርባዋ በርካታ ሰው ተከትሏታል፣ ድምጿን ከፍ አድርጋ ትጮሃለች፣ ህዝቡ እንደ ገደል ማሚቶ እየተቀባበለ ያስተጋባል።

"ሌሊቱ - ወልዷል ፈረሷም - ወልዳለች! ሌሊቱ - ፈርዷል ፈረሷም - ወልዳለች!" ትጮሃለች፤ "ባሌን ልቀቁልኝ? የልጆቼን አባት ፍቱልኝ!" ትሮጣለች፣ ትጮሃለች። ህዝቡም ተከትሎ ይሮጣል፤ ይጮሃል! ያስተጋባል!።

ቁና ቁና እየተነፈሱ አብረዋት የሚሮጡት ወንድና ሴት ልጆቿ፤ አንድ የፈረስ ግልገል ተሸክመዋል . . . **ባለ ሁለት ጭንቅላት ነበር!።**

"ሌሊቱ እርጉዝ ነበር - ያረገዘውን እውነት ወለደ፣ ያለ አግባብ የፀናውን የተንኮል ውሳኔ የሚሽር ሃቅ ፈረደ። ፈረሷም እርጉዝ ነበረች፤ ሊሆን አይችልም በሚል እኩይ ተስፋና አይደረግም በሚል ጽኑ ምኞት፣ በእውነት ላይ የተቃጣውን ሞት የሚያረክስ፤ ባለ ሁለት ጭንቅላት ግልገል በሆድዋ ነበር፤ በትክክለኛው ሰዓት ወለደችው። "ሌሊቱ እርጉዝ - ፈረሴም እርጉዝ!" ያለው ለዚህ ነበር። ይባላል፡፡

"ምንግዜም እውነትን ያዙ! የእውሸት መንገድ ሁሌም ጊዜያዊ ነው። አያዛልቅም፡፡ የተንኮል ሴራ፣ ሃሰትና ምቀኝነት በምንም አይነት ሃቅን የማሸነፍ ብቃት ኖሯቸው አያውቅም፤ የላቸውም፤ ወደፊትም አይኖራቸውም።"

**የጸሃፊው ማስታወሻ፡-** በርካታ መሳጭ ተረቶችን እየነገሩ ያሳደጉን አባታችን ግራዝማች ጴጥሮስ ዮሣ፤ ጥር 13 1985 ዓ. ም. ከዚህ ዓለም ቢለዩንም እነሆ የለገሱን ጥልቅ ፍቅርና የተረኩልን መሳጭ ተረቶች፣ በልባችን ውስጥ ይኖራሉ። እንደ እግዚአብሄር ፈቃድ ዘርፈ ብዙ እምቅ እውቀታቸው፣ በራሳቸው ብዕር ተዘርቶ ቢሆን? እልና ውጤቱን ሳስብ፣ የእግር እሳት ቢሆንብኝም ያልታተሙ ሥራዎቻቸውን ለንባብ እንድናበቃ፣ ቸሩ ፈጣሪ እድሜና ብርታቱን አይንፈገን እላለሁ።

ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ



**"ጓደኝነት"**

ቦታው ቅልጥ ያለ ውጊያ የሚካሄድበት የጦር ግንባር ነው። ጥቃት የበረታበት ወገን ሽቅብ የተራራውን ሰንሰለት ተከትሎ ይነጉዳል ። (ሽሽት ወይም በስልት ቅየራ ራስን ማዳን ልትሉት ትችላላችሁ)። በዚህ ምስቅልቅል መሃል አጉል ቦታ በጥይት ተመትቶ የወደቀ ጓደኛውን ለማንሳት ወደ ኋላ መለስ ያለው ወታደር በአዛዡ ቁጣ አዘል ትእዛዝ ደንግጦ ቆመ።

"የሱ ነገር በቃ - ስለማይተርፍ ማምጣት አያስፈልግም . . . ተወው፤ ባለበት ይረፍ !" አሉት።

በማይታጠፍ የአለቃ ትእዛዝና በጓደኝነት ዳራ መንታ ጽንፎች የተወጠረው ወታደር አዛዡን ለማሳመን የቻለውን ያህል ወተወተ። ይህ ሁሉ ሲሆን የተራራ ጉዟቸው ለአፍታም ሳይገታ እየገሰገሱ ነበር። ተስፋ ያልቆረጠው ወታደር በመጨረሻ ተሳካለትና ነብሱን በጓደኝነት ፍቅር ለውጦ ቁልቁል አልፎት ወደመጣው የሞት ቀጣና ተንደረደረ።

ቀንቶት ከስፍራው ደረሰና ጓደኛውን አነሳው። ለብቻ የሚፈትነውን አቀበት ጓደኛውን ተሸክሞ እንደምንም በመፍጨርጨር ዳገቱን ጨረሰና ባሻገር ጦሩ ያረፈበት ደልዳላ ቦታ ላይ ደረሰ ። አውላላው ሜዳ ላይ የተጋደመውን አስከሬን ያስተዋሉት አዛዡ . . .

"አላልኩህም? ለማይረባ ነገር መልፋትና መባከንህ አላስፈለጊ ነበር፣ ዋጋ የሌለው ከንቱ ድካም ነው - ሞቷል" አሉት። ሰውነቱ ተሸማቀቀ፣ እንባውን ለመቆጣጠር በሚያደርገው ትግል ፊቱ እያበጠ የሚሄድ መሰለው።

የጓደኛው አስከሬን ላይ እንዳቀረቀረ "ጌታዬ ዋጋ አለው! ለኔ የባከነም ሆነ ከንቱ ድካም አልነበረም ይልቅስ እጅግ የከበረ፣ ከሁሉም የላቀና ፍሬአማ ነበር "በማለት እንባ እየተናነቀው ቀጠለ "ጌታዬ በጨለማው እየተደነቃቀፍኩ ቁልቁለቱን ወርጄ ጥሻው ስር የተዘረረው ጓደኛየ ጋ ስደርስ፣ ቀና ብሎ አየኝና ከውስጡ በሚፈልቅ መንፈስ ፈገግ ብሎ የመጨረሻዎቹን ቃላቶች ተናገረ። ምን እንዳለኝ ያውቃሉ? . . . **"ተመልሰህ እንደምትመጣ እርግጠኛ ነበርኩ!"** መቀጠል አልቻለም . . . ስቅስቅ ብሎ አለቀሰ።

እውነት ነው! በፍጹም ከንቱ አልነበረም። "ተመልሰህ እንደምትመጣ እርግጠኛ ነበርኩ" ይህ ብዙ ብዙ የማይጠገቡ ቁም ነገሮች የሚመዘዙበት እጅግ ታላቅ ዓረፍተ ነገር ነው። በተለይ ጫፍ የደረሰ እምነቱን ላረጋገጠው ቁስለኛም ሆነ አደራውን በብቃት ለተወጣው ጓደኛ የሚኖረውን ትርጉምና ምሉእ እርካታ አስቡት። እኔ እነሱን ሆኜ አሰብኩትና ኀሊናዎቻቸው ብእር ጨብጠው የልባቸውን በሥነ ግጥም ቢገልጹ ሊሉ የሚችሉትን አልኩላቸው። እነሆ . . .

**የቁስለኛው ወታደር (ኅሊና) በመጨረሻው ሰአት . . .**

ከተረተሩ ኢጋማሽ - ከጉድባው በታች ተጋድሜ
አይኖቼ ሽቅብ አፍጥጠው - በጠራው ሰማይ ተደምሜ
የቁስሌን ህመም ዋጥ አድርጌ - እንዳልተደረገ ትቼው
መውደቄን ላለመቀበል - ላለማስታወስ ረስቼው
የልቤን በልቤ ይዤ - በምናቤ ልክ እያስታወስኩ
እኔን ከኔነቴ ነጥዬ - በሃሳብ ባቡር ተሳፈርኩ

የኑሮ ጉጉትም ሆነ - ሞትን ፈርቼ አላውቅም
ወቶ አደር ስሆን ተቆርጧል - ዳግም አይከለስም
ግና ለማይቀር ህልፈት - በማይድን ቁስል መታመም
በስቃይ ጥፍር መቧጠጥ - በሱስ መሽበር ይቀርም

እግሬን መሄድ ተስኖት - ከጥሻው ጥጋት ወድቄአለሁ
ጥይት ጎኔን በድሶት - አይሆኑ ሆኜ ቀርቻለሁ
አሸዋው በደሜ ርሷል - ክፉኛ ተጎድቻለሁ
አልሞትኩም ግን ወደዚያው ነኝ - ሕይወትን እናፍቃለሁ

ወትሮ ባራዊት ጬኸት - በነብሳት ፂርታ የሚደምቀው
የሳር ቅጠሉ ሽታ - ዙርያ ገባውን የሚያውደው
ዛሬን በጥይት ናዳ - በባሩድ ጠረን ተቀበለው
ብቸኝነት ወረረኝ - አካሌን ድካም አዛለው
ጓዶቼም ዳናቸው ራቀ - ህልፈትን ሊያልፉ በመላ
ሞት እያባረራቸው - ደረስኩ እያለ ከኋላ

ጎጆ አልባው ሌጣ መሬት - አሁን አርፏል ተረጋግቷል
ጫካው ደኑና ሸንተረሩ - ዝምታ ውጦት ፀጥ ብሏል
ብቻውን አይደለም ዛሬ - የሚያድርበት ሰው አግኝቷል
ሞቱን ታግሶ ሚጠብቅ - ጥቁር እንግዳ መጥቶበታል

በዚህ ሁሉ መከራ ውስጥ - በድቅድቅ ጽልመት መዳረሻ
ጭጋግ ባጠረው ፍትህ መሃል - ባበቃ ጥረት መጨረሻ
ቅንጣት ብልጭታ ቀርታኛለች - የሰለሰለች ትንሽ ተስፋ
በጓደኝነት ቃል አብባ - በፍቅር ኪዳን የምትፋፋ
እሷን ባልሰንቅ ባልመካ - የመንፈስ ጽናት ባትመግበኝ
መታገሴም ህልም ነበር - መሰንበቴንም አልመኝ

ልቤ ወስኖ ካፀናው - ከ አእምሮዬም ድምዳሜ

ውስጤን ካረጋጋው መንፈስ - ከማይዋልለው አቋሜ
ይበልጥ እምነት ነበረኝ - ባንተ ላይ ኮርቶ የከበረ
ቅንጣት የማይጓደል - እስከ ጫፍ ዘልቆ የኖረ

ትተኸኝ እንደማትጓዝ - መጥተህ እንደምትወስደኝ
ምንም ሳላወላውል - እርግጠኛ ነበርኩኝ
ይኸው ተመካሁብህ - አንተም አላሳፈርከኝ
መንፈሴን ሃሴት መገብካት - ደስታን አጎናፀፍከኝ

ውቅያኖስ መሃል ተጥዬ - በሞት የሸረት ማእበል
አየሁ በህልሜ ስትጣጣር - እኔን ለማትረፍ ስትታገል

አቤት እንዴት ደስ ይላል . . . ያለሙት ቅን ህልም ሲሳካ
ያመኑት በቦታው ሲገኝ - ፍቅር በጽናት ሲለካ
ያኖሩት ያደራ መንፈስ - በልብ ያነጹት የእምነት ቃል
ያሰቡት እንደ ገመቱት - ሲሆን ምንኛ ደስ ይላል ፡፡

ውዴ ! አንተን ካየውህ - ከጎኔ ሆነህ ከደገፍከኝ
ባልተርፍም ተመችቶኛል - ተጋሁ ፍጹም ደህና ነኝ
አሁን ሺ ሞት ይምጣና - ይደርደር ከ ፊት ለፊቴ
መንገድ መደቤ ተደላድሏል - አልጨነቅም ለህይወቴ

አቤት እንዴት ደስ ይላል . . . ያለሙት ቅን ህልም ሲሳካ
ያመኑት በቦታው ሲገኝ - ፍቅር በጽናት ሲለካ
ያኖሩት ያደራ መንፈስ - በልብ ያነጹት የእምነት ቃል
ያሰቡት እንደ ገመቱት - ሲሆን ምንኛ ደስ ይላል ፡፡

. . . ይል ነበር ፡፡

<u>በሌላ በኩል፤ አፋፍ ላይ ሆኖ በሃዘን የሚተክዘው የጓደኛው ኀሊና ደግሞ . . .</u>

ገና በጠዋት ከጥንስሱ - ላገር ክብር ስንሰለፍ
ለመሰዋት ቃል ስንገባ - በትግሉ ሥር ስንሳተፍ
ላገር ክብር ዘብ ስንቆም - አቅማችን ሁሉ በቻለው
መግደል መኖሩን ተረድተን - መሞት እንዳለም አውቀን ነው

በጠላት አረር ተመተህ - ክልትው ብለህ ስትደፋ
ስትቀርብን ተነጥለህ - ስንበተን ያለ ተስፋ
እልህ ሲቃው በረበረኝ - ጎንህ ሳልሆን በመከራ
ልቤን ትቼልህ ወርውሬው - በድኔን ወጣሁት ያንን ጋራ

ባለቃና በወንድም ፍርድ - በመንታ ግብር መሃከል
ከፍቅርና ከትዛዝ ቃል - አንዱን ለማንሳት ስዋልል
የውስጤን ቁርጥ ማሳመኑ - ምንኛ ፈታኝ መሰለህ ?
አንተም አልጠፋህ እውነቱ - በደምብ አርገህ ታውቀኛለህ፡፡

ሕልፈትህን አሜን ብዬ - ትቼው ቀርቼ በነበር
እድሜ ልኬን ስቀጠቀጥ - በፀፀት ጠንካራ በትር
ምንኛ ስቃይ ነበረ - የሕሊና ላይ ጠባሳ
አብሮኝ የሚኖር ፀያፍ ነገር - ጊዜ ፍቆትም የማይሳሳ

ለጓደኛውም ያልሆነ - አደራ በላ እምነተ ቢስ
የከደት አጋ ፋሪ - የገባውን ቃል የሚያፈርስ
ከመባል የከፋ ቁስል - ባጉል ስያሜ መነሳት
ምን ይገኛል የሚያሳፍር - መሪር ሃዘን የቁም ውርደት

ድካሜ መና አልነበረም - ልፋቴም ከንቱ አልባከነም
ይልቅስ ውጤታማ ነው - አብሮኝ የሚኖር ለዘላለም

የውስጥህን ቅን እሳቤ - አስረግጠህ ስትነግረኝ
እንደ ብስራቴ ቆጠርኩት - እምነትህ ኩራት ዘራብኝ

ይገቡህ እንደምወጣ - እንደማቀናህ - አውቀኸው
እንደምመለስ ተማምነህ - ፍቅራችንን አፀደከው

ድካሜ መና አልነበረም - ልፋቴም ከንቱ አልባከነም
ይልቅስ ውጤታማ ነው - አብሮኝ የሚኖር ለዘላለም

. . . እንደሚል ቅንጣት አልጠራጠርም።

መነሻ ታሪክ ፡- ከአጫጭር የሥነ ምግባር ጽሁፎች ስብስብ www.moralstories.org - ("Friendship")
ጥቅምት - 2008 አዲስ አበባ

**"ከእናቴ የቀሰምኩት"**



ድሮ ነው ገና ልጅ እያለሁ፣ እናቴ አንድ ጥያቄ ጠየቀችኝ። ጥያቄው - "ከሠውነታችን ክፍሎች እጅግ አስፈላጊው የትኛው ነው?" የሚል ነበር። በየጊዜው ማስረጃ አጣቅሼ እሰጣት የነበሩትን የተለያዩ መልሶች ዛሬ ላይ ሆኜ ሳስባቸው ግርም ይሉኛል።

የመጀመሪያው መልሴ "ጆሮ ነው" የሚል ነበር ምክንያቱም በልጅነት መንፈሴ ነገሮችን ለመግለጽ ድምጽ ዋናው መንገድ በመሆኑና የሚደመጠውም በጆሮ ስለሆነ ነበር። እማማ ግን "አይደለም! ብዙ ሰዎች መስማት ሳይችሉ እንደማናችንም ይኖራሉ አይደል ? አስብበት በቅርብ ጊዜ ደግሜ እጠይቅሃለሁ" በማለት መልሱን እንዳላገኘሁ ነገረችኝ።

ደግማ ሳትጠይቀኝ ዓመታት አለፉ። እኔ ግን ትክክለኛውን መልስ ለማግኘት ዘወትር አስብና አሰላስል ነበር። አንድ ቀን ጥያቄውን አነሳችልኝ፤ እኔም "እማዬ በእርግጠኝነት ማየት ዋነኛ ነገር ነው - ስለዚህ አስፈላጊው አካላችን ዓይናችን ነው አልኳት። አተኩራ እየተመለከተችኝ "በፍጥነት እየተማርክ ነው ነገር ግን መልስህ ትክክል አይደለም፤ ብዙ ማየት የተሳናቸው ሰዎች በአይናቸው ምክንያት ወደ ኋላ ሳይሉ ከኛ ከዓይናማዎቹም በተሻለ ስኬት መዝለቃቸውን አላስተዋልክም?" አለችኝ።

ከዚያ ወዲህ ሁለት ሦስቴ ጠይቃኛለች፣ እኔም በተለያየ መንገድ ግንዛቤየን እያዳበርኩና ምክንያቶችን እያነሳሁ የሰጠኋቸው መልሶች ትክክል ባይሆኑም "ውድ ልጄ! በየጊዜው በአካል እያደክ፣ በአስተሳሰብህም እየበሰልክና ምርጥ እየሆንክልኝ መጥተሃል" ትለኝ ነበር። እንዲህ እንዲህ እያልን ቆየንና አምና በዚህ ወር ይመስለኛል አያቴ በድንገት አረፉ። ቤተሰባችን ጥልቅ ሃዘን ላይ ወደቀ። ሰው

ሁሉ ያለቅሳል፣ አባቴ፣ ጎረቤቶቻችን፣ ዘመድ አዝማዶቻችን እንደው ሁሉም መሪር ሃዘን ላይ ነበር። የአያቴ የመጨረሻ ስንብት ደረሰና ከእናቴ ጎን እንደሆንኩ ወደ መቃብሩ ስፍራ ስናመራ "የኔ ልጅ - እስካሁን እጅግ አስፈላጊው የሰውነታችን ክፍል የትኛው እንደሆነ አልተረዳህምን?" ስትል ጠየቀችኝ።

ደነገጥኩ! በዚህ ሰአት ለምን እንዳነሳችብኝ አልገባኝም፤ ነገሩን በእርሷና በእኔ መካከል የሚደረግ ቀለል ያለ ውድድር አድርጌ ነበር የማየው። የፊቴን መቀያየር እንዳስተዋለች እንዲህ በማለት ታብራራልኝ ጀመር።

"ይህ በጣም አስፈላጊ ጥያቄ ነው፣ የግል ህይወትህን በትክክል እየኖርክ እንደሆነ ተገንዝቤአለሁ። ከዚህ በፊት የሰጠኸኝ መልሶች ለምን ስህተት እንደሆኑም በምሳሌ አስደግፌ ስነግርህ ቆይቻለሁ። ዛሬ ግን ትክክለኛውን ትምህርት የምትቀስምበት ቀን ዛሬ ነው "አለችኝና እጄን ያዝ አድርጋ ወደ ጉያዋ አስጠጋችኝ። ሁሌም በዚህ አይነት እቅፍ ስታደርገኝ ለመግለጽ የሚያስቸግር ፍጹም የሆነ ብርታትና ጽናት ይሰማኛል፣ ቀና ብየ አየኋት . . . የእናት ብቻ በሆነ አስተያየት ቁልቁል ተመለከተችኝ፣ አይኗ እንባ አቅርሯል . . . ቀጠለች - "የኔ ውድ ! እጅግ በጣም አስፈላጊው የሠውነታችን ክፍል . . . <u>ትከሻችን ነው</u>" አለችኝ።

ገረመኝ "ትከሻችን - ራሳችንን ስለሚሸከምልን ነው?" በማለት ጠየኳት። እሷም

"አይደለም - በሃዘናቸውና በመከፋታቸው ጊዜ የጓደኞቻችንን እና የወዳጆቻችንን . . . ራስ ስለሚሸከም ነው ። ሁላችንም በሕይወታችን ውስጥ ስናዝን የምንደገፍበትና ሽጉጥ ብለን የምናለቅስበት ትከሻ ያስፈልገናል። ሃዘንና መከራ የተጫነው የወዳጆቻችን ጭንቅላት ክብደቱን የሚጋራና ሸክሙን የሚያሳርፍበት መጠግያ ይፈልጋል፣ ለዚህ ደግሞ እንደ ትከሻችን የሰጠ የለም። ውድ ልጄ ! - አንተም በክፉ አጋጣሚ በፈለካቸው ጊዜ ሊሸከሙህ የሚችሉ የጓደኞችህና የአፍቃሪዎችህ በቂ ትከሻዎች እንዳሉህ አምናለሁ። ልጄ . . . ትከሻችን የክፉ ጊዜ ብቻ ሳይሆን በደግም ቢሆን ደስታቸውን በይፋ የሚገልጹበት በእንባና ሳግ የታጀበ ስኬታቸውን ድግፍ ብለው የሚያጋሩበት ምቹ አካል ነው" በማለት አብራራችልኝ።

እነሆ ፡ - ከዚያን ጊዜ ወዲህ እጅግ በጣም አስፈላጊው የሠውነታችን ክፍል ራስ - ወዳድ ሳይሆን ርኅሩኅ፣ ሌሎችን የሚረዳና ህመማቸውን የሚሸከም፣ ለእኛ ብቻ ሳይሆን ለሌሎች የተፈጠረ ቅን መሆኑን ተገነዘብኩ።

“People will forget what you said. People will forget what you did . But people will NEVER forget how you made them feel”

“ሰዎች የተናገርከውን ይረሱታል፡፡ ያደረግኸውንም ይዘነጋሉ፡፡ በውስጣቸው የፈጠርክባቸውን ስሜት ግን ፈጽሞ አይረሱትም፡፡”

ምንጭ - ማኅበራዊ ድረ ገጽ “The Most Important Part of our Body”
Rohan Pinto best Moral Stories collection pdf Elect book
ግንቦት 2006 አዲስ አበባ

## <u>ከ አጥሩ በስተጀርባ</u>

አንድ ለአትክልትና ለአበቦች ልዩ ፍቅር የነበራት ሴት ነበረች። ከልጅነቷ አንስቶ አብዛኛውን ጊዜዋን በአትክልት ስፍራዋ የተለያዩ እጽዋትን በመትከልና የግቢዋን አበቦች በመንከባከብ የምታሳልፍ ሲሆን ይህንን ባህሪይ ካወረሷት አያቷ በርካታ ትምህርቶችን ቀስማ ስለነበር በአካባቢው ከአያቷ ቀጥሎ ድንቅ የተባለ የአበባ ስፍራ ለመፍጠር ችላለች።

ይህችው ታታሪ ሴት አልፎ አልፎ ወጣ እያለች የተለያዩ የአበባ አምራቾችን እርሻ የመጎብኘት ልማድ ነበራት። እናም ከእለታት በአንዱ ቀን ጉብኝቷ አንድ ለየት ያለ አበባ አይኗን ማረከው። "እንዲህ የሚያምር አበባ ያለው ተክል በአትክልት ስፍራዬ ውስጥ ቆሞ ማየት አለብኝ" በማለት በእልህ ለራሷ ቃል ገባችና የተባለውን ዋጋ ከፍላ እንዲያመጡላት አዘዘች። ከጥቂት ቀናት በኋላ ችግኙ እንደደረሳት የግንብ አጥሯን መሰረት ተጠግቶ ቀደም ብላ ባዘጋጀችለት ቦታ ተከለችው።

እንክብካቤ ያልተለየው ተክል አረንጓዴ ቅጥያዎች ያሉት ወፍራምና ጤናማ አንጓ አወጣ። የሚያምሩት ቅጠሎች ዙርያውን እየበዙ እየፋፉና እድገታቸው እየጨመረ ቢመጣም አንዳችም እንቡጥ አበባ ሳያፈሩ ብዙ ጊዜ ቆዩ። ልጅቷ በየቀኑ በመኮትኮት እንዲሁም በቂ ውሃና ምግብ በመስጠት በተቻላት ሁሉ ብትንከባከበውም ምንም ለውጥ ማየት አልቻለችም። በበዛ ትእግስት ጠብቃ የጓጓችለትን እንቡጥ አበባ ባለማየቷ ቅሬታዋ ጨመረ፣ ተበሳጨች። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ አንድ ቀን በጠዋት ተነስታ የተክሉን ረጅም ሃረግ ከስሩ ቆርጣ ለመጣልና በምትኩ ሌላ ነገር ለመትከል ወስና ትልቁን መቀስ ይዛ ወጣች።

ይህ በእንዲህ እንዳለ እምብዛም ቀረቤታ ያልነበራቸው ጎረቤቷ ከአጥሩ በስተጀርባ ሆኖ ሲጠራት ሰማች። ድምጹን ከፍ አድርጎ "እጅግ በጣም አመሰግናለሁ! የተከልሽው ልዩ የሆነ የወይን ሃረግ ተክል ያፈራቸው እጅግ በርካታ እንቡጥ አበባዎች የሰጡኝ ደስታ መገመት ከምትችይው በላይ ነው! - በእውነት አመሠግንሻለሁ" አላት። ለማመን አልቻለችም። ፈጠን ብላ በዋናው በር ወጣችና ዞራ ወደ ጎረቤቷ ቤት አመራች። የአዋሳኝ ጎረቤቷ ግቢ በወደር የለሹ የአባባ መአዛ ታውዷል። ያ የናፈቀችው እንቡጥ አበባ መስኩን

ሞልቶና እዚህም እዚያም ጎምርቶ ስታይ አይኗን ተጠራጥራ ጨፈን - ከፈት ጨፈን - ከፈት . . . በማድረግ አተኩራ አየችው። በቃ - በእውኗ የምታስተውለው ትክክል እሱ ራሱ ነው፣ ግቢዋ ውስጥ የተከለችው፣ በናፍቆት ስትጠብቀው የቆየችው፣ ያለመታከት ስትንከባከበው የከረመችው ተክል . . . ከድንጋዩ ግንብ ስር ከአጥሩ በስተጀርባ ረጅም ሃረጉን አሾልኮ ጎረቤቷ ግቢ ውስጥ ተኝቷል። የጓጓችለት አበባ በየቦታው ፈክቶና በማደግ ላይ ባሉ ትንንሽ ፍሬዎች ታጅቦ ድንበርተኛዋ መስክ ላይ ተረፍርፏል። በሷ በኩል ግን ምንም - ምንም . . . አበባም ሆነ ፍሬ የለም።

ተክሉን ከስሩ ቆርጣ ጨርሶ የማጥፋት ሃሳቧን ስታስታውስ ቁጣዋን የሚያበርድና ደስ የሚል ስሜት አጥለቀለቃት። "እንኳኔም ኣላደረኩት . . . ቆርጬ ጥየው ቢሆን - ምንኛ እፀፀት ነበር?። የተመኘሁት እምቡጥ በሌላ ግቢ ማፍራቱ ሊያስከፋኝ አይገባም፣ በአበባውና በውጤቱ ጎረቤቴ ከተደሰተ . . . በእኔ በኩል ያለው ሥር እንክብካቤ አይጓደልበትም፤ መደረግ ያለበት ሁሉ እንደ ነበረ ይቀጥላል . . . ።" በማለት ለራሷ ቃል ገባች።

ወዳጆቼ! - የልፋትና ጥረታችሁ፣ የድካምና ክትትላችሁ ውጤት ወይም መጨረሻ ሁሉ ምንጊዜም እንደተመኛችሁት ባሻችሁና በፈለጋችሁት ስፍራ ላይገኝ ይችላል። ይህ ግን ተሰናከለ ማለት አይደለም። አልተሳካም ማለትም አይደለም። አበው፡ "የትም ፍጪው፣ ዱቄቱን አምጪው" ይላሉ ቁም ነገሩ የእህሉ መድቀቅ እንጂ የትም ይፈጭ የት ከጉዳያችን አይገባም ለማለት ነው። በመልካም ጥረት የሚገኝን በጎ ውጤት ራሳችን ለመቀዳጀት እንሻለን፣ የግኝቱን እፍታ ልንቋደስ በመጎምጀት ወጥነን ልንንቀሳቀስም እንችላለን - እሰየው ቀና ህልም ነው። ነገር ግን ውጤቱ አልፎን ወይም ቀድመነው ለሌላ ትውልድ አልያም ቦታ ጥቅም ሲሰጥ የሚያስኮርፈን ከሆነ ይህ ነው ከፉ በሽታ፣ ይህ ነው መታከም ግድ የሚለው የአመለካከት ችግር።

ዘመነኛ ልክፍት ተጠናውቶን በእጅጉ እየናጠን ያለው፣ ባልተገራ የራስ ወዳድነት ፈረስ ሽቅብ ቁልቁል የሚጋልበን አርቆ አለማሰብ ነው። ለትውልድ አለማለምና አሻግሮ አለማየት፣ ሙገሳ ታይታና ግላዊ ጥቅምን በመሻት፣ ዛሬን ለዛሬ ብቻ በማሰላት ጥበብ እኛው ዘርተን - እኛው አጭደን - ወቅተን - ፈጭተን - አቡክተን - ጋግረን - ወጥውጠን፣ ሌማቱ እርቃኑን፣ ጎተራው ባዶውን እስኪቀር አግበስብሰን ስናበቃ ትርፍራፊ ወዝ እንኳ እንዳይሸተው ትሪውን ቧጠን እስከመጨረሻው እንጥፍጣፊ የምንበላ እኩዮች በበረከትንበት ዘመን ዜማችን "እኔ ከሞትኩ - ሰርዶ አይብቀል" - መፈክራችን ". . . እኔ በደከምኩት የሚበላው ሌላ" በሚል የምቀኝነት ቅላጼ የተቃኘ ሆኗል።

በእርግጥ መድከምና መጣርህ የሚያስመሰግን ቀና ተግባር ነው ነገር ግን አንተ ከደከምክ የግድ አንተ ብቻ መብላት አለብህ ያለው ማነው? ያውም ጥርግ አርገህ ያሳፍራል!። በማሳፈር ብቻም አያበቃም የቀደመው ምግባርህን የሚያረክስ ፀያፍ ድርጊት ነው። በዚህ መንገድ ሥራችን ዘመን ተሻጋሪና እዚህም እዚያም ባልተመጠነ መዳረሻ ካልፈሰሰ፣ ትልማችን ሁሉንም የሚያቅፍና የሚያሳትፍ ሆኖ እቅዳችን መጪውን ሁለት ሦስት ተከታታይ ትውልድ በሚያገለግል መልኩ ካልተነደፈ፣ ከድጡ ወደማጡ መንከላወስ ደንበኛችን እንደሆነ ሊቀጥል ነው።

እያንዳንዳችን ከዚህ ፀያፍ ባህሪ ፈጥነን መላቀቅና ዛሬን ለነገ ከነገወዲያ ማነጽን፣ ለኛ ሳይሆን ለሌሎች መኖርን፣ ካልተገቡና አሳፋሪ ተግባራት በመራቅ የብዙሃንን ጥቅም ማስከበርና እውነትን በእውነት ማምለክ . . . ጊዜ ሳንሰጥ የግድ መልመድ አለብን። ይህ ባለንበት ዘመን፣ የታሪክንና የለወጥ ሂደትን መዘውር ለምናስረክበውም ሆነ ለሚቀበለው ባለ አደራ ትውልድ ከምንም ከማንም በላይ ትኩረት የሚሻ ወሳኝ ጉዳይ ነው። ይሁን እንጂ የስህተቶቻችንና የደካማ ጎኖቻችን ብርቱ መንስኤ መሆኑን እያወቅን እንኳ . . . ምላሻችን ምንምና ምንም ነው። አንድ ነገር ይጠበቅብናል . . . አርቀን ማስተዋል - ሰዎች ከእንስሳት የምንለይበት ሰብአዊ መለኪያም ይኸው ነው።

ደራሲ፡ ራንዲ ሬይኖልድስ * ምንጭ፡ (Roger Darlington's World) ~ የካቲት - 2008

## "ባርኔጣ ነጋዴው"





ነገሩ የተፈፀመው ቀደም ባለው ጊዜ ነው። እንዲህ ሆነላችሁ . . . አንድ ባርኔጣ ነጋዴ ነበር። ይህ ሰው በየሣምንቱ የተለያዩ ባርኔጣዎችን ባሻገር ከሚገኘው ከተማ እየገዛ በመንደሩ ገበያ በመሸጥ ሲተዳደር ኖሯል። ከእለታት አንድ ቀን እንደተለመደው ባርኔጣዎቹን በቅርጫት ተሸክሞ ጫካውን በማቋረጥ ላይ ሳለ ደከመውና አንድ ትልቅ ዛፍ ጥላ ሥር ለማረፍ ቅርጫቱን አጠገቡ አስቀምጦ ጋደም አለ። በዚያው ጭልጥ ያለ እንቅልፍ ወስዶት ቆየና ድንገት ያልተለመደ ድምጽ ቀስቅሶት ተነሳ። ወዲያው ወደ ቅርጫቱ ቢዞር ምንም ባርኔጣ የለም፣ ባዶ ሆኗል። ደነገጠ! ባርኔጣዎቹን ሁሉ ማን ለቃቅሞ ወሰዳቸው? እየተዟዟረ ፈለገ ምንም የለም። ድንገት ወደላይ ሲመለከት ብዙ ዝንጀሮዎች የዛፉን ቅርንጫፎች ሞልተው ተቀምጠዋል። እያንዳንዳቸው ያደረጉት ባለ ልዩ ልዩ ቀለማት ባርኔጣ ትልቁን ዛፍ የገና ፅድ አስመስሎታል።

በመገረም አፉን ከፍቶ ቀረ፡፡ ከግርምቱ ሲወጣ በዝንጀሮዎቹ ያለአግባብ የተወሰደበት ንብረቱን እንዴት እንደሚያስመልስ ማሰብ ጀመረ፡፡ ከብዙ ማውጣትና ማውረድ በኋላ ድንገት አንድ ሃሳብ ብልጭ አለለት፡፡ ሰውዬው ጊዜ አላጠፋም፡፡ ወዲያው ሃሳቡን ተገበረ፡፡ መጀመሪያ ራሱ ያደረገውን ባርኔጣ አወለቀና (ለዝንጀሮዎቹ እያሳየ) ራሱን አከክ አከክ አደረገ፡፡ ሁሉም ዝንጀሮዎች ሰውዬው

ያደረገውን ደገሙት። የመጀመርያ ሙከራው በመሳካቱ በልበሙሉነት የተሞላው ነጋዴ ወደ ቀጣዩ ሙከራ ተሸጋገረ፡፡ በእጁ የያዘውን ባርኔጣ አሽቀንጥሮ ወረወረው። ሁሉም ዝንጀሮዎች በፍጥነት ባርኔጣቸውን ወደ ታች ወረወሩ፡፡ ሰውዬው ባርኔጣዎቹን ከወደቁበት ሰብስቦ ቅርጫቱ ውስጥ ከተተና ብልሃቱ ባጎናጸፈው ኩራት ታጅቦ ጉዞውን ጀመረ፡፡

ይህ ታሪክ አብዛኛዎቻችን እድሜአችን የአርባውን አጋማሽ የዘለለ ሁሉ ያኔ በዘመናችን በአንደኛ ደረጃ ት/ቤት የአማርኛ መማርያ መጽሃፍ ውስጥ ያነበብነውን "ጦጣዋና ተማሪው" የተሰኘ ታሪክ ያስታውሰናል ብዬ እገምታለሁ፡፡ ተሳሳትኩ?። ለማንኛውም ታሪኩን በአጭሩ ላስታውሳችሁ፡፡ አንድ ተማሪ ቁጭ ብሎ ሲጽፍና ሲያጠና ጦጢት ሆዬ ዛፍ ላይ ቁጭ ብላ ሁሉን ነገር ትከታተላለች፡ ፡ ከዚያም ተማሪ አገር አማን ብሎ ነፋስ ሊቀበል ዞር ሲል፣ ከዛፉ ላይ ትወርድና የተሜ ደብተር ላይ በእስክሪብቶ ትሞነጫጭራለች፡፡ በዚህ ክፉኛ የተናደደው ተሜ፤ በጦጢት ላይ ተንኮል ያስባል፡፡ እያየችው አንገቱን በዶሮ ላባ ይገዘግዛል፡፡ ለዕረፍት ሲሄድ ግን በላባው ፋንታ ቢላዋ ነው የሚያስቀምጥላት፡፡ ጦጢት ከመቅጽበት ከዛፉ ላይ ዱብ ትልና፣ ተማሪው ሲያደርግ ያየችውን ትደግመዋለች፡፡ ብልጢት ጦጣ ትሸወዳለች፡፡ አንገቷን በቢላ ገዝግዛ ራሷን ትገድላለች፡፡

በዚህ ታሪክ ልጆችን ምን ለማስተማር ታስቦ የአማርኛ መጽሐፍ ውስጥ እንደተካተተ ፈጣሪ ይወቀው፡፡ እዚህ የእኛው ታሪክ ላይ ከብልሃቱ ይልቅ ተንኮሉ ስላየሉብኝ ምን ለማስተማር እንደተፈለገ አልገባኝም? ያኔም አልጠየኩም፣ እውነቴን ነው የምላችሁ ጥያቄው የመጣልኝም አሁን ነው ከአርባ አመታት በኋላ፤ የባርኔጣ ነጋዴውንና የዝንጀሮዎቹን ታሪክ ሳነብ።

አደራ ! እንዳይሰለቻችሁና ንባባችሁን እንዳታቋርጡ። አሁንም እርግጠኛ ነኝ! ሁላችንም ታሪኩ አበቃ፣ ተጠናቋል ብለን አስበን ነበር። ለካንስ አላለቀም . . . ቀጥሏል። እነሆ - አብረን እንጨርሰው።

ባርኔጣ ነጋዴው አረጁ። ከሃምሳ አመት በኋላ ማርከ የተባለ የልጃቸው ልጅ እንደ እርሳቸው ባርኔጣ ነጋዴ ሆነ። አያት ለልጃቸው ልጅ ብዙ ተረቶችንና ገጠመኞቻቸውን ሲያጫውቱት፤ የዝንጀሮውን ታሪክም ነግረውታል። ከእለታት አንድ ቀን ልክ እንደ አያቱ ባርኔጣዎቹን ተሸክሞ በዛው ጫካ ውስጥ ሲጓዝ ደከመው፣ ቅርጫቱን አጠገቡ አስቀምጦ ጥቂት ለማሸለብ የአባቱ አባት ከዓመታት በፊት ያረፉባት ዛፍ ስር ጋደም አለ።

ከእንቅልፉ እንደነቃ ያስተዋለው ባርኔጣዎቹ በሙሉ መወሰዳቸውን ነበር። በአይኑ ግራና ቀኝ በማማተር ላይ ሳለ የሆነ ድምጽ ሰማና አቅጣጫውን ተከትሎ ቀና ሲል ሁሉንም ባርኔጣዎች ዝንጀሮዎቹ አድርገዋቸዋል። ወዲያው አያቱ የነገሩት ታሪክ ትዝ አለው . . . ጊዜ አላጠፋም፣ እራሱን አከከ አከከ አደረረገ። ዝንጀሮዎቹም እሱ እንዳደረገው ራሳቸውን አከኩ። ቀጠለና ባርኔጣውን ከፍ አድርጎ አወዛወዘ . . . ዝንጀሮዎቹም ደገሙት። ማርከ የአያቱ ዘዴ ሙሉ ለሙሉ እንደሚሰራ በመተማመን ባርኔጣውን መሬት ላይ ወረወረው። . . . ጠበቀ . . . ጠበቀ . . . ከእነሱ በኩል ምንም ባርኔጣ አልተወረወረም።

በግርምት አፍጥጦ እየጠበቀ ሳለ አንድ ዝንጀሮ ከዛፉ ላይ ዘሎ ወረደና እርሱ መሬት ላይ የጣለውን ባርኔጣ አንስቶ አደረገ። (ባርኔጣ ያልደረሰው ዝንጀሮ መሆን አለበት) ማርከ ፈዞ እንደቆመ ዝንጀሮው ጠጋ ብሎ አንድ ጥፊ አቀመሰውና. . .

<u>"አያት ያለኝ እኔ ብቻ ነኝ ብለህ ታስባለህ?"</u> ብሎት እየሳቀ ዛፉ ላይ ወጣ። ይባላል።

ወዳጆቼ - ሁሌ መብለጥ፣ ሁሌ ማታለልና ማሞኘት አይቻልም። የራስን አቋም በማግዘፍ ሌሎችን ከመጠን በታች ዝቅ አድርጎ ማየት፣ በትናንት ዘዴ ዛሬን ለመድገም ማቀድና ብቃታቸውን አውርዶ መገመት ጠንቅ አለው። "ስትሄድ ያደናቀፈህ ድንጋይ ስትመለስ ከደገመህ፤ ሌላ ማንም አይደል ድንጋዩስ አንተ ነህ" የተባለው ምሳሌ ለተቃራኒ ወገን የምንሰጠው ዝቅተኛ ግምት እንደ ባርኔጣ ነጋዴው ማርከ ዋጋ እንደሚያስከፍል ለማመላከት ነው።

ሰዎችን አንዴም ሁለቴም . . . እንደውም ደጋግመን ልንዋሻቸውና እያታለልናቸው እንደሆነ ልናስብ እንችላለን። ለዚህ ከልካይ የለንም። ነገር ግን ውሸታችንን እስከምን ድረስ እንዳመኑትና እንደተቀበሉትም ሆነ ምን ያህል እንደታለሉልን እርግጠኛ የምንሆንበት መንገድ የለም። ምክንያቱም የሚያዳምጡን አማራጭ አጥተው ሊሆን ይችላል፣ የተሞኙልን የሚመስሉትና ፊት ለፊት የማይቃወሙን ምናልባት ስለሚፈሩን ይሆናል፣ እና ሌላም ሌላም . . .። እኛ ግን ሳንቀንስ – እየጨመርን፣ ሳናቋርጥ – እየደጋገምን እንቀጥላለን። ለምን? ለሌሎች በምንሰጠው የወረደ ግምትና ሁሌም እያታለልንና ተቀባይነትን እያገኘን ያለን ስለሚመስለን ነው። ከዚህ ይሰውረን !።

አንድ የገረመኝን ነገር ላውጋችሁ፣ የኛው ተረት የምሩን አልቆ ነበር። ይህንን ግን ከፈረንጆቹ መጽሃፍ በቋንቋቸው ተጽፎ ሳነብ የተረትና ምሳሌዎች አለም አቀፋዊ መመሳሰል አስገረመኝ። ድሮ ድሮ በልጅነቴ ንባብ የተማርኩባት የ "ጦጣዋና ተማሪው" አስኳል መልእክት ሚዛን ባይደፋልኝና ሌሎች ያስታወስኳቸው የመማሪያ ታሪኮቻችን እነ "ተንኮለኛው ከበደ" ሸክላ ድስትና የብረት ድስት" ወዘተ . . . የሚያስተላልፉት መልእክት ከመብለጥ፣ ከማታለልና ሌላውን ከማሞኘት አልሻገር ቢሉ "ምነው እኛ ነን እንዴ ተረት ሳይቀር እንዲህ የምናጣምመው?" አሰኘኝ።

በፈረንጆቹ ተረት ላይ "ማርከ ከሃምሳ አመት በፊት አያቱ ያሸለቡበት ዛፍ ስር እሱም ልክ እንደ እርሳቸው አንቀላፋ" ይላል። ድንቅ ነው "በአንድ ጠጠር ሁለት ወፍ" መበለጥ እንዳለ ለማሳየት ብቻ ሳይሆን እድሜ ጠገብ ዛፎችን ጠብቆ ለትውልድ ስለማስተላለፍም ሰብኳል እላለሁ። አይ ምስኪኑ ማርከ እኛጋ ቢሆን ምኑ ስር ይተኛል? ምናልባት ጉቶው ላይ ይቀመጥ ይሆናል እንጂ። እሰይ - አሪፉ ነገር ግን ዛፎቹን ቆርጠን ስላጠፋናቸው ዝንጀሮዎቹም አይኖሩምና ባርኔጣው ሳይወሰድ፣ ጉቶው ተርፎ ካለ እሱው ላይ ቁጭ ብሎ፣ በሰላም አርፎ ይሄድ ነበር ። የምን ጥላ ሥር መተኛት?።

"100 Meaningful Stories collection"
"MONKEY and THE HAT SELLER"
ኅዳር - 2006 * አዲስ አባባ

## **"ራስን መዳኘት"**

"ጥፋተኛው ማነው?"፣ "ኃላፊነቱን የሚወስደው ማነው?"፣ "ተጠያቂው ማነው?" . . . ሌላም ሌላም መሰል ጥያቄዎች በዘወትር ውሏችን፣ በሥራም ሆነ በሌላ የእርስ በእርስ ግንኙነታችን ውስጥ የሚነሱ ናቸው። እኒህ በስፋት የበጎ ተቃራኒ ለሆነ ጉዳይ በመንስኤነት የሚቀርቡ መጠይቆች በሰዎች ሕሊና ላይ የሚያሳድሩት ተጽእኖና የማይዳሰስ ጠባሳ ግምት ባይወጣለትም የመረዳትና የመረዳዳት መንፈስን ስለ መሸርሸራቸው ምስክር አያሻውም። የሚከተለው አጭር ታሪክ "ራስን መዳኘት" የቆየ  አመለካከታችንን ዞረን እንድናስተውል መንገድ ይከፍትልናል።

ጥንዶቹ መተሳሰብ ከሰፈነባቸው አሥራ አንድ የትዳር ዓመታት በኋላ ወንድ ልጅ - ከነቃጭሉ ዱብ አለና ጎጇቸውን በደስታ ብርሃን አደመቀው። የሚዋደዱት ባልና ሚስት የአይናቸው ማረፍያ እምቡጥ ፍሬ የወሬአቸው ማሳረግያ፣ የጨዋታቸው ማጣፈጫ እንደሆነ አንድ ብሎ የሁለተኛ ዓመት ልደቱን አከበረ። ይህ ከሆነ ጥቂት ወራት እንዳለፉ አንድ ጠዋት አባት ሥራ ለመሄድ ይዘጋጃል። በመሃሉ ጠረጴዛው ላይ ክፍቱን የተቀመጠ መድሃኒት አየና ለሚስቱ መድሃኒቱን ከድና ቁም ሳጥኑ ውስጥ እንድታስቀምጥ ነግሯት ተቻኩሎ ወጣ።

የቁርሱን ጉዳይ ከውና ልጇ ከእንቅልፉ ሳይነቃ የጽዳትና የምሳውን መሰናዶ በከፊል እንኳ ለማያያዝ ኩሽና የገባችው እናት የመድሃኒቱን ነገር እርስት አድርጋው ተፍ - ተፍ ስትል ቆየችና ትዝ ሲላት ወደ ሳሎን ብር ር ር ብላ ሄደች። ፈጣኑ ልጅ ሳሎን ጠረጴዛው አጠገብ ቆሟል። ደማቅ አረንጓዴ ቀለም የነበረው የመድሃኒት ብልቃጥ ባዶውን ተጋድሟል፣ ማሙሽ እናቱን ሲያይ ቅጠልያ ወዝ ያደመቀው ከንፈሩን ሾጠጥ አርጎ በፈገግታ ተኮላተፈ። እናት በቆመችበት አዞሯት ተውተርትራ የበሩን መቃን ተደገፈች፣ ጉሮሮዋ ደርቆ ቃላት ከአፏ መውጣት ተሳናቸው። እንደምንም ተንደርድራ ልጇን ተሸከመችና በሩን አልፋ ወደ ጎዳናው ሮጠች። ከዚያም ወደ ሆስፒታል።

ለአዋቂዎች የሚያገለግል መድሃኒት ለህፃናት አደገኛ መርዝ የሚሆንበት አጋጣሚ ብዙ ነው። ሰውነታቸው ሊቋቋመው ስለማይችል ለከፋ ጉዳት ሊዳርጋቸውና ሕይወታቸውን ሊቀጥፍ ይችላል። ሆስፒታል የደረሰው ህፃን ምንም ሊረዳ አልቻለም፣ ጥቂት ቆይቶ ሕይወቱ አለፈች። አቤት . . . እናት የሆነችውንና የደረሰባትን ሃዘን የሚገልጽ ቃል የለም። እንደ በረዶ ቀዝቅዛ፣ እንደ ሃውልት ደርቃ ቆማለች። የልጅ ህልፈት፣ ፀፀትና የጥፋተኝነት ስሜት፣ ቁጭትና ድንጋጤ . . . ሰባብረዋታል፣ ባሏን እንዴት እንደምታየው ስታስብ ደግሞ ላብ አጠመቃትና ተንቀተቀጠች።

የአንድያ ልጁን አደጋ ሰምቶ ወደ ሆስፒታል የሚገሰግሰው አባት ብርክ ይዞት እየተንገዳገደ ደረጃውን ጨርሶ ከክፍሉ ደረሰ። . . . . ቀና አለች፣ እንባ በሚዘራው የአይኗ ጭጋግ ስር የባሏን ድንጋጤ ያገረጣው ፊት አየች። ወዲያ ወዲህ ይቃብዛል በድንገተኛ

የሕፃናት ክፍል ውስጥ ባዶውን አልጋ ከበው የቆሙ የሚያውቃቸውንም የማያውቃቸውንም ሰዎች መልክ አስተዋለ፣ አዎ - ሁሉም ነገር አልቋል፣ ልጁን . . . አወቀው።

እናት እንደ እሳት የሚፋጀውን የባሏን ገጽታ የመመልከት ወኔውም ሆነ ችሎታው ከድቷት ሄዷል፣ አይኗን ጨፈነች። በዚያች ሰዓት የሞት አይነቶች ሁሉ ተሰልፈው ቢወስዷት ምኞቷ ነበር፣ የምትደፍረውም እሱን ብቻ። ግን አልሆነም ቀስ ብላ አይኗን ከፈተች። የሙብረቅ ፍላፃ . . . ፊት ለፊት ተያዩ፣ የሚከተለውን እንደማትቋቋመው አውቃለች፣ እርሷ ብቻ ሳትሆን ክፍሉ ውስጥ ያሉት ሁሉ ትንፋሻቸውን ውጠው በሳግ ታፍነዋል . . . ፀጥ እረጭ።

ከ አባ ወራው አፍ ያፈተለኩ አራት ቃላት እንደ ቦንብ ፈነዱና ፀጥታውን አደፍርሰው አየሩ ላይ ናኙ። . . . እስካሁን እዛው ባሉበት የሚኖሩ ይመስለኛል።

እዚህ ላይ ጽሁፌን ልግታና እንድትገምቱ ጊዜ ልስጣችሁ ።

<u>ጥያቄ አንድ፡ ባሏ ምን አለ?</u> (ምን ሊል እንደሚችል ገምቱ)።
<u>ጥያቄ ሁለት፡</u> አባባሉ የሚያስከትለው ተጽእኖና የመጨረሻ ውጤት ምን ይሆናል ትላላችሁ እስቲ ይህንንም ገምቱ?።

ግምቶቻችሁን አስቀምጣችሁ ካበቃችሁ በኋላ የሚቀጥለው ገጽ ላይ የሆነውን (መልሱን) ተመልከቱ።



"አ ይ ዞ ሽ - ፍ ቅ ሬ - ሁ ሌ ም - አ ወ ድ ሻ ለ ሁ" በትክክል ያለው ይህንን ነበር ።

ወደፊት ተራመደና ግድግዳው ጥግ አቀርቅራ የቆመች ሚስቱን በስስት እቅፍ አደረጋት። ራስዋን እያሻሸ በትኩስ የእንባው ዘለላዎች የተኮማተረ ፊቷን አበሰው። ፊቷን ብብቱ ስር ሸጉጣ ለመጀመሪያ ጊዜ ድምጿን አውጥታ አለቀሰች። ዳግም ለማያገኙት እንቦቃቅላ ልጃቸው አብረው - አነቡ . . . ተያይዘው አለቀሱ።

"አይዞሽ - ውዴ - ሁሌም - አፈቅርሻለሁ" የአራት ቃላት ስብስብ አንድ ቀላል የሚመስል ዓረፍተ ነገር። በዚህ ሰዓትና ሁኔታ ግን ሊጠበቅ ቀርቶ ሊታሰብ የማይሞከር ተአምር፣ ፈውስ የሚዘራ አስደማሚ ቃል። ባሏ ግን አለው - ተናገረው። ድርጊቱ ምናልባት በሰው ልጆች ግንኙነት ውስጥ የበሳል አእምሮ የመጨረሻው ደረጃ ላይ ሊያስቀምጠውና አስተውሎት የታደለ የመጀመሪያው አፍቃሪ ባልም ሊያደርገው ይችላል። ልጃቸው አልፏል፣ በምንም ዓይነት ሊመልሰው አይችልም። ታድያ ስህተት መፈለግና እናቱን ተጠያቂ ማድረግ ምን ይፈይዳል?።

እውነቱን ለመናገር እርሷም እኮ ብቸኛ ልጇን አጥታለች። በዚህ ወቅት የሚያስፈልጋትና የምትሻው ሃዘኗን የሚጋራ፣ ከጎኗ የሚቆምና የሚያጽናናት የኔ የምትለው ሰው ነው። ውድ ባሏ ያደረገውም ይህንኑ ነው። የህይወትን መደበኛ ገጽ በዚህ መንገድ የምንረዳ ጥቂት ሰዎች እንኳ ብንኖር፤ ከዓለማችን ውስብስብ ችግሮች ከፊሎቹ ባልተፈጠሩም ነበር ያሰኛል። "ከወንድ ጋር በደስታ አብሮ ለመኖር የግድ በጥቂቱ አፍቅሮ በአብዛኛው ስለሱ መረዳትን ይጠይቃል። ግን ከሴት ጋር በደስታ አብሮ ለመኖር በአብዛኛው ስለሷ መረዳትና በሙሉ ልብ ማፍቀርን ግድ ይላል"። የሚል የቆየ አባባል አለ። "የአንድ ሺህ ማይል የርቀት ጉዞ በአንድ እርምጃ ይጀመራል"። ለሰመረ የእርስ በርስ ግንኙነትና ስኬት የማስመሰልን ጭምብል አውልቆ መጣል፣ ምቀኝነትን፣ ቂመኛነትን፣ ራስ ወዳድነትን እና ቅናትን ጨርሶ ማስወገድ ያስፈልጋል።

ወዳጆቼ! ይብዛም ይነስ በእለት ተእለት ግንኙነታችን ውስጥ ግጭቶች ከሠላማዊው ሁኔታ ባልተናነሰ መጠን ይከሰታሉ። ይህ ጥልቅ ጉዳይ የእያንዳንዳችንን ጓዳ በለሆሳስም ይሁን በጠንካራው የሚያንኳኳ በመሆኑ እስቲ በጥቂቱ ዙሪያችንን እንቃኝ።

ሁልጊዜ ለተፈጠሩ ስህተቶችም ሆነ ለተፈፀሙ ጥፋቶች የቅድሚያ እርምጃችን ምክንያትና ሰበብ ማበጀት ሲሆን ሁሉም ምክንያቶቻችን የሚያጠነጥኑትና የመጨረሻ ግባቸው ደግሞ ሌላውን ተጠያቂ ማድረግና በተቻለ መጠን ራስን ነፃ ለማውጣት መጣር ነው። መንስኤዎችን ማጣራትና ማወቅ ለወደፊት እርምት፣ ጥንቃቄና ትምህርት አስፈላጊነታቸው እጅጉን የላቀ መሆኑ ባያጠያይቅም

በዚህ መስመር የምንፈጥራቸው - "ጥፋተኛው እሱ ነው"፣ "ተጠያቂዋ እርሷ ነች"፣ "ኃላፊነቱን የሚወስዱት እነርሱ ናቸው" . . . ወዘተ ምክንያቶች እኛ የምናውላቸው በተቃራኒው መንገድ ሌሎችን ለመኮነንና ጥፋቶችን ለማላከክ በመሆኑ ባብዛኛው ጥፋታችንን የምንደበቅባቸው ዋሻዎች ከመሆን አይዘሉም።

ለተፈፀመና ላበቃለት ክስተት በየአቅጣጫው ሰበብና ሰለባዎችን መደርደር ከማሳዘን ያለፈ ፋይዳ እንደሌላቸው እስቲ በሃገራችን የትዳር ጓደኛሞችን ከሚያጋጩ ዝርዝር መንስኤዎች ጥቂቶቹን እንይ። አብዛኛዎቹ ሚዛን የማይደፉና እዚህ ግባ የማይባሉ ናቸው። ጥቂት ባለመታገስ፣ በሰከነ ባህሪ ባለመወያየትና በመሳሳሉት አባባሽ ምክንያቶች የተነሳ ከመፍረስና ከመበታተን አልፈው ጊዜ ለማይሽረው የሕሊና ስብራትና እስከ ባሰባቸው በርካታ አሰቃቂ አደጋዎችም ይዘልቃሉ።

በፖሊስ እንዲሁም በሌሎች ወንጀል ነክ ዜናዎችና የቴሌቪዥን ዝግጅቶች እንኳ እንደዘበት የምናያቸው እስከ ሕልፈት ለሚደርሱ ወንጀሎች እንደ ምክንያት የሚነሱት እጅግ ተራና አሳዛኝ ጉዳዮች ናቸው "ልጄን እራት ሳታበይው ተኛ"፣ "ልብሱን በደንብ አላጠብሽለትም"፣ "የቤት ሥራዋን ሳታሰሪያት መሸ"፣ "የሥራሽው ቁርስ አልጣፈጠኝም" አልያም "በውድቅት ለሊት ስመጣ ተኝተሽ ጠበቅሽኝ" . . . ወዘተ መንስኤ ሚስቱን የሚነተርክ፣ ዱላ መዞ ያለርህራሄ የሚቀጠቅጥና ከአካል ማጉደል እስከ ነፍስ ማጥፋት የሚደርስ ባል ሞልቶ በተረፈበት አገር ጉዳያችን ከአንገብጋቢነትም አይብስ ትላላችሁ?። እና - ይህም አለ። በትንሽ በትልቁ ሰበብ በመፍጠር፣ የጥፋትን ልክ ሁሉ ለሌላ ሰው በማሸከምና ራስን ዞር ብሎ ባለማየት ከአምባጓሮ አልፎ በሚፈጠር አጓጉል ጀብደኝነት የደረሰውን ስንትና ስንት ጥፋት ቤት ይቁጠረው። ሰለባዎቹ እናትና እህቶቻችን ስለመሆናቸው ደግሞ ማስረጃ የማይጠይቅ እውነታ ነው።

ባለታሪኩ ባል ለሚስቱ በሰጠው ወደር የለሽ ይቅርታና ምሕረት አዘል ፍቅር ውስጥ በርካታ የማይታዩ አብይ ፈለጎች አሉ። በቅን ሕሊና ራስን መዳኘት የሚያስፈልገውም እነሱን ለማየት ነው። አሊያ አይታዩም። ልጁ የሞተበት አባት በዚያ የመከራ ሰአት ራሱን የፈተሸበት ሕሊና የተባለ መነጽር "መድሃኒቱን እርሷ እንድታነሳው ከመንገር እኔ ባነሳውስ? መጀመሪያውኑ እዛ ባላስቀምጠውስ ኖሮ? ልጄን ላልመልሰው ሃዘን ያደቀቃት ባለቤቴን መኮነን ምን ይጠቅማል? . . . ወዘተ" የተባሉ በሌጣው አእምሮ የማይታዩ እውነታዎችን አየ። በአግባቡ ተገነዘበና በአንድ ሃያል አረፍተ ነገር ከሚስቱ ጎን እንደሚቆም አረጋገጠ። እጅግ ድንቅና ታላቅ ድርጊት፣ ወደር የለሽ ውሳኔ።

በቅን ሕሊና ራስን የመዳኘት ዋጋም ይኸው ነው። በአብዛኛዎቻችን ውስጥ የጎደለና በገሃድ የሚታይ ክፍተት፣ እያለን ያላወቅነው፣ ተጽፎ ያላደመቅነው የሕይወት መስመር፣ ያልተረዳነውና ምሉእ የሚያደርገን የሕሊና መነጽር - እውነት። እስቲ ስንኝ ልደርድርለት . . .

**"አይዞሽ - ፍቅሬ - ሁሌም ወ ድ ሻ ለ ሁ !"**

የሃዘን በትር ላረፈበት - የፀፀት እዳ ለከበደው
አካል ገላው ተሸማቆ - የእንባ ጭጋግ ለጋረደው
በጥፋት ናዳ ለሰመጠ - የቀን ጨለማ ለዋጠው
አብራኩን በሞት ለተቀማ - ሆድ ለባሰው የሰው ሰው

ሲቃውን ከማደስ በቀር - ሰበብ ምን ይበጀዋል ?
ቁስሉን ማባባስ እንጂ - ምክንያትስ ምን ይጠቅመዋል ?

በፍቅር ሚዛን የተለካ - ራሱን በእውነት የዳኘ
ከህሊናው ሥር የሚያስተውል - በምግባሩ ልክ የተቃኘ
ጋሻ፣ መከታ፣ ወንድም፣ ባል - አጽናኝ ከጎኑ ያለው ሰው
እሱ ብቻ ነው መዳኑ - ተረጋግጦለት የሚኖኘው ።

"አይዞሽ - ፍቅሬ ውዴ - ሁሌም ወድሻለሁ !"
"ህመምሽን በመታመም - ጥቃትሽን እጋራለሁ"
"መከራሽን በመሸከም - ሲቃዬን ውጬ ትቻለሁ"
"የመጣውን ለመቀበል - ይኸው ከጎንሽ ቆሜአለሁ"

አ ቤ ት . . . ! ! !
ከዚህ የላቀ ጥኡም - ሃያል የከበረ ቃል
የመንፈስ ምግብ ገበታ - ከቶ ከወዴት ይገኛል ?

የቅን ህሊና ወጌሻ - ሰባራ ቅስምን የሚያክም
የፍቅር ዜማ ቅላጼ - ከጽኑ ፀፀት የሚያስገግም
የጉዳት ፍቱን መድሃኒት - የፈውስ ብርሃንን የሚዘራ
የትዳር ምሰሶ ማገር - የሕይወት ሰብል አዝመራ

"አይዞሽ ማሬ - ውዴ - ሁሌም እወድሻለሁ !"
"ህመምሽን እታመማለሁ - ጥቃትሽንም እጋራለሁ"

ከዚህ የላቀ ጥኡም - ሃያል የከበረ ቃል
የመንፈስ ምግብ ገበታ - ከቶ ከወዴት ይገኛል

ይህስ ቃል ብቻ አይደለም - ልሂቅ ነው እጅግ የላቀ
እስከ ፍፃሜው የሚበራ - ከረቂቆችም የረቀቀ።

ምንጭ፡ ከሥነ ምግባር ትምህርቶች ድረ ገጽ www.moralstories.com
ደራሲ፡ ያልታወቀ ርዕሥ፡ "Treasure what you have"
ሰኔ 2008 *** አዲስ አበባ



**"የሕይወት - ቅመሞች"**

ጃፓኖችና ትኩስ የዓሣ ጥሬ ሥጋ ፍቅር መቼም ተወርቶ የሚያልቅ አይደለም፣ የምንግዜም ነው። (የእኛን ጥሬ ስጋ መውደድ ቢበልጥ ወይ ቢመጥን እንጂ አይተናነስም)። ድሮ ድሮ ጥልቁ ውኃ ከየብሱ ሳይርቅና ዓሣው እንደልብ በሚገኝበት ጊዜ የትኩስ ዓሣ አቅርቦት የሚጠቀስ ችግር አልነበረበትም፣ በአመታት ቆይታ ሁኔታዎች መልካቸውን ቀይረው ለዓሣ አስጋሪዎች ከባድ ፈተና እየሆኑ መጡ። የሕዝቡን ፍላጎት ማርካት የዋዛ አልሆነም። በተለይ የጃፓናውያን ቁጥር አንድ ተወዳጅ ምግብ "ሱሺ" ዋና ዋና ግብአት የሆኑት የአሳ አይነቶች - ማጉሮ፣ አምበርጃክ፣ ቶሮ፣ ሃማቺ ፣ሳልሞንና . . . የመሳሰሉትን የአዓሣ ዝርያዎች አድኖ በትኩሱ ለማቅረብ ረጅም የባህር ላይ ጉዞ የግድ ስለነበር በቆይታው የገረጡት ዓሳዎች ሥጋ ትኩስና ተፈላጊ መሆን አልቻለም።

ይህንን ችግር ለመፍታት አንድ ነገር ማድረግ ነበረባቸውና ታታሪዎቹ ዓሳ አስጋሪዎች አንድ ብልሃት ተጠቀሙ፤ . . . ትልልቅ ማቀዝቀዣዎችን ጀልባቸው ውስጥ ገጥመው ዓሣዎቹን እንደነበሩ በማቆየት የተፈለጉበት ስፍራ ያደርሷቸው ጀመር። በዚህ ሁኔታ ለተወሰነ ጊዜ የሰራው በበረዶ ቤት አቀዝቅዞ የማጓጓዝ ዘዴ ብዙም ሳይዘልቅ ተፈላጊነቱ እየቀነሰ እያደር ዋጋውም እያዘቀዘቀ መጣ።

ይህ ሲሆን የጃፓናውያኑ ፋታ የለሽ አእምሮ ሌላ መፍትሄ ወለደ። ማቀዝቀዣውን የሚተኩ የውኃ ገንዳዎች ተዘጋጁና ዓሣዎቹ እየዋኙ ይጓዙ ዘንድ ሁኔታዎችን አመቻቹ። ይህ ድንቅ ሙከራ ዓሣዎቹን ከነሕይወታቸው ቢያደርስም እንደተፈለገው መዋኘት ግን አልቻሉም። ለጥቂት ደቂቃ ተንቀሳቅሰው ወዲያው አንድ ቦታ ላይ ይከማቻሉ። አፋቸውን የገንዳው ጠርዝ ላይ አስጠግተው እንደደነዘዙ የሚቆዩት ዓሣዎች ከመተንፈሳቸው በስቀር የሞቱ መስለው ነበር የሚጓዙት። እነዚህ ጡንቻዎቻቸው የተሳሰሩና በዝለት የወየቡ ዓሣዎች ትክክለኛውን የትኩስ ጥሬ ዓሳ ጣእም በመያዝ ተወዳጆቹን ባህላዊ ምግቦች መመጠን አልቻሉም። ስለዚህ ቀሪውን ክፍተት የሚሞላ አንድ ወሳኝ ፈጠራ ማምጣት ነበረባቸው።

ጃፓናውያኑ ዓሣ አስጋሪዎች ምን አይነት መፍትሄ ያበጁ ይሆን?። እስቲ እንያቸው።

ባላሰለሰ ጥረታቸው መጨረሻ ዓሣዎቹ በረጅሙ የገንዳ ውስጥ ቆታቸው እየዋኙና እንደልባቸው እየተንቀሳቀሱ በንቃት የሚጓዙበትን ድንቅ ስኬት ተቀዳጁ። አንድ ትንሽ ሻርክ ያዙና የአሳዎቹ ገንዳ ውስጥ ከተቱት። ጨዋታው ተጀመረ . . . የሻርኩ አደን፣ የዓሣዎቹ ሽሽትና ራስን የመከላከል ሂደት፤ ገንዳውን ሕይወት ዘራበት። ጥቂቶቹ መበላታቸው እንዳለ ሆኖ ከጥግ ጥግ እየዋኙና በንቃት እየተሯሯጡ ረጅሙን ጉዞ ያገባደዱት ዓሣዎች ቁልጭ እንዳሉ ከታሰበበት ደረሱ። በዚህ አይነት የሻርኩ መኖር በፈጠረው የሕይወት ፍልሚያና ላለመረታት በሚደረግ የውድድር ስሜት፤ ትክክለኛው ትኩስ የዓሣ ምርት ለደንበኞቻቸው ይደርስ ዘንድ አስቻላቸው። ይባላል።

ወዳጆቼ - በቀላሉ እንደው እንደዘበት መኖር ቢቻል ኖሮ ሕይወት ምን ያህል አሰልቺና ትርጉም የለሽ ትሆን እንደነበር አስባችሁ ታውቃላችሁ?። እውነታው ፍጹም ከምንገምተው በላይ ነው። ውጤቱ እጅግ ውስብስብ ከመሆኑም በላይ ምናልባት ኖረን ይህንን የመጠየቅ እድል ባላገኘንም ነበር። ችግሮችና የመፍትሄ ጥረቶች የሕይወት እርምጃ መሠረቶች ናቸው። የተቃራኒ ሃይል ግፊት፣

የሞት ሽረት ትንቅንቅ፣ ላለመሸነፍ የሚደረግ ውጣ ውረድ፣ ፉክክር፣ ውድድር፣ ትግል፣ ፈተናና . . . . ወዘተ ሁሉም አይነተ ብዙ ስልቶች፤ የኑሯችን አካሎችና ወሳኝ ቅመሞች ናቸው። ሕይወትም ያለእነዚህ ሁኔታዎች ግኡዝ፣ ፈዛዛና አስጠሊታ በሆነች ነበር።

የሻርኩ መኖር የገንዳውን ሕይወት እንደቀየረው ሁሉ የእኛም ሕይወት፣ የእኛም ልዩ ልዩ ተቋማት፣ የእኛም አመለካከትና ነባራዊ ሁኔታ መስኩን የሚያተጋና የሚቀሰቅስ አካል ይፈልጋል፣ ዙሪያ ገቡን የሚያነቃና የሚያነቃንቅ ቀና አስተሳሰብ፣ ግግሩን የሚያቀልጥ - ፍርክርኩን የሚያገጣጥም፣ ከወዲያ ወዲህ የሚንጥና ለተሃድሶ የሚያነሳሳ አመለካከት ይሻል። ይህንን ወዶና ፈቅዶ ማምጣት፣ መቀበልና የእውነት መሳተፍ ቀላል ባይሆንም የለውጥ ድንቅና ብቸኛው አማራጭ ነው።

"ምቀኛ አታሳጣኝ" "ጠላትና የደጅ ላይ አረም . . . "ወዘተ በርካታ ተረቶች የዋዛ መልዕክት አያስተላልፉም። "አሯሯጮች" (pacemakers) በሩጫው የውድድር መስክ ውስጥ የሚፈጽሙትና የሚፈለጉበት ጉዳይ ከዚህ የተለየ አይደለም። ወራጅ ውኃ በተጓዘ ቁጥር ንጽህናው እየጠራ የሚመጣውም ለዚህ ነው። ፏፏቴውን እየዘለለ፣ አሸዋው ስር እየተሽለኮለከ ከድንጋይ ድንጋይ እየተጋጨ . . . መሄዱ (መፍሰሱ)።

በሁሉም ዘርፍና አቅጣጫ ተቃራኒ አመለካከቶች፣ ጠያቂና ፈታሽ ሃሳቦች፣ የጥናት ውጤቶችና የምርምር ግኝቶች፣ ተቃዋሚ ፓርቲዎችና ምክኒያታዊ ተቋማት፣ ሃያስያን፣ ተራማጅና ባለራዕይ ምሁራን፣ አላማና ግብ ያላቸው መናንያን፣ ፊት ለፊት የሚጋፈጡ ሰብአውያን፣ ደፋርና ጠንካራ ሰባኪያን፣ አድማጭና ተግባሪ ምእመናን . . . ወዘተ የግድ አስፈላጊ ናቸው . . . ። ህፀፆችን ነቅሰው የሚያፋጥጡና የእርምት አቅጣጫዎችን የሚያመላክቱ፣ ጉድለቶችን መርምረው የሚያጋልጡና የመፍትሄ ፍንጮችን የሚያቋድሱ . . . ፈር ቀዳጅ የሕዝብ ልጆች መኖር ከላይ እስከታች ለሚታሰቡ በጎ ስኬቶች ሁሉ ግድ የሚሉ የኛዎቹ አሣ ነባሪዎች ናቸው. . . የሕይወት ቅመሞች።

*"Man thrives, oddly enough, only in the presence of a challenging environment"* — L. Ron Hubbard

**ምንጭ : www.All Time Short Stories.com**
**"Sharks in Life"** **ታህሳስ - 2008 (ዓ. ም.) * ኢጋሮ**

## በድፍኑ አትፍረዱ

ዶክተሩ ተንቀሳቃሽ ስልኩን በመጀመሪያው ጥሪ አነሳ ". . . ሃሎ!"

"ሃሎ . . . ዶክተር እባክህ አስቸኳይ ቀዶ ጥገና የሚያስፈልገው ህመምተኛ ስለመጣብን ታስፈልገናለህ?"

ምንም ጊዜ ሳያባክን ወደዛው ገሰገሰ፣ የሆስፒታሉን ቅጥር ግቢ በሩጫ አቋርጦ ቢሮው በመግባት ልብሱን ቀየረና በፈጣን እርምጃ ቀዶ ጥገናው ሕንፃ ውስጥ ሲገባ የታማሚውን አባት ፊት ለፊት አገኘው። እሱን ጥበቃ ክፍሉ ውስጥ ወዲያ ወዲህ ሲንጎራደድ የነበረው አባትም ገና እንዳየው በቁጣ አምባረቀበት . . .

"ይህን ያህል ሰዓት እንዴት ትዘገያለህ?፣ የልጄ ህይወት ምን ያህል በአደገኛ ሁኔታ ውስጥ እንዳለ ይገባሀል? ከቶ ምንም አይነት የሃላፊነት ስሜት አይሰማህም?" አለው።

ዶክተሩም በፈገግታ "በጣም አዝናለሁ፣ ሆስፒታሉ ውስጥ አልነበርኩም፣ መልእክቱ እንደደረሰኝ እንደምንም ብዬ በምችለው አቅም ፈጥኜ መድረሴ ነው፣ እናም ፍቃድህ ሆኖ አንተም ብትረጋጋና ወደ ህክምናው ብገባ ይሻላል" ሲል መለሰለት።

"ብትረጋጋ ? ተረጋጋ ትለኛለህ እንዴ ደግሞ? - እዚህ ክፍል ውስጥ የተኛው ያንተ ልጅ ቢሆን ኖሮ አንተ ትረጋጋ ነበር? አሁን የገዛ ልጅህ እዚህ ቢሞት ምን ትላለህ?" በማለት በቁጣ ጠየቀው።

ዶክተሩ - አሁንም ፈገግ እንዳለ "እኔ . . . እኔ የምለውማ በቅዱሳን መጽሃፍት እንደተጠቀሰው አፈር ነንና ወደ አፈር እንመለሳለን ነው። የአምላክ ስም የተባረከ ይሁን፤ ዶክተሮች ህይወት አይቀጥሉም - እባክህ ሂድና ስለ ልጅህ ፀልይ፣ እኛ ከፈጣሪ ጋር በምንችለው ሁሉ እንጥራለን፤ ሃያሉ አምላክ በፀጋው ይደግፈን" አለው።

አባትየው "ያልደረሰበት ምክር ለመስጠት ይቀለዋል" በማለት እያጉረመረመ።

ከጥቂት ሰአታት በኋላ ቀዶ ጥገናው ተጠናቆ ዶክተሩ ከክፍሉ ሲወጣ በደስታ "አምላካችን የተመሰገነ ይሁን ልጅህ ተርፏል" አለውና ምንም መልስ ሳይጠብቅ እየተራመደ መውጫው በር አጠገብ ሲደርስ "ለማንኛውም ጥያቄ ነርሷን አነጋግራት" ብሎ በፍጥነት ወጥቶ ሄደ።

ዶክተሩ እንደወጣ የልጁ አባት - "ለምንድነው ይህ ሰው እንደዚህ እብሪተኛ የሚሆነው? ስለ ልጄ ሁኔታ ለመጠየቅ እያሰብኩ ጥቂት ደቂቃ እንኳን መቆየት አልቻለም" አላት ነርሷን እያየ።

ከመጀመሪያው አንስቶ እዛው የነበረችው ነርስ አይኖቿ እንባ እንዳቀረሩ እንዲህ አለችው፡- "ዶክተር ልጁ ትናንትና በመኪና አደጋ አረፈበት፣ ቅድም ላንተ ልጅ ቀዶ ጥገና ስልክ ስንደውልለት የቀብሩ ሥነ ሥርአት ላይ ነበር፤ እናም መጥቶ ከፈጣሪ ጋር የልጅህን ነብስ አተረፈልህ፣ ከዚያም እንዳየኸው አቋርጦ ወደመጣበት የቀብር ሥነ ሥርአት ተመለሰ። ለልጅህ አይነት እጅግ ውስብስብና አፋጣኝ ቀዶ ጥገና የከተማችን ብቸኛ ስፔሻሊስት እሱ ብቻ ነው" ። አለችው።

አባትየው የሚለው አልነበረም  ዝም - እንደው -  ዝም . . . ብቻ።

ሳታረጋግጡ በድፍን አትዳኙ! አትፍረዱ! ምክንያቱም ስለ ሰዎቹ ህይወትም ሆነ ስላሉበት ሁኔታ ምንም አታውቁምና ሁሌም ለትችት አትቸኩሉ !።

ምንጭ፡ ከሥነምግባር ትምህርቶች ማህበራዊ ድረ ገጽ
(STORIES TO MAKE YOU THINK Collection) - “Think Before You Judge”
የካቲት - 2006 ዓ.ም.





## "ራስን መሆን"

ጊዜው ጥንት ለመባል የሚበቃ በአስራ ስምንተኛው ምእተ አመት አጋማሽ ሲሆን ቦታው ጃፓን - ዮኮሃማ ነው። በመልካም ባህሪውና በጀግንነቱ የታወቀው ጃፓናዊ አርበኛ (ሳሙራይ) አንድ ቀን በማለዳ ተነስቶ ወደ መነኩሴው ቤት ገሰገሰ። መልስ ያጣለትን ጥያቄ በሆዱ እያብሰለሰለ ሲጓዝ ቆይቶ ፀሃይዋ ሳትከር ካሰበበት ደረሰና መነኩሴው የጠዋት ፀሎታቸውን እስኪያጠናቅቁ ግቢው መሃል ከምትገኘው የዘንባባ ዛፍ ጥላ ስር አረፍ ብሎ ይጠብቃቸው ጀመር። ሰፊው ቅጥር ግቢ እንደ እርሱ መነኩሴውን ለማነጋገር በመጡ በርካታ ምክር ፈላጊ ሰዎች ተሞልቷል። መነኩሴው ፀሎታቸውን እንደጨረሱ የተረዳው ሳሙራይ ራመድ ራመድ ብሎ ወደ መነኩሴው ተጠጋና በቀጥታ ጥያቄውን አቀረበ።

"እንደሚታወቀው ሃገሬን በጀግንነት አገልግያለሁ፣ ግን ለምንድነው ዝቅተኝነት የሚሰማኝ? ለምንድነው የምሳቀቀው?። እልፍ ጊዜ ሞትን ፊት ለፊት ተጋፍጫለሁ፣ ለተገፉ፣ ለተበደሉና ለደከሙ ሰዎች በመቆም አደራየን በብቃት ተወጥቻለሁ ሆኖም ዛሬ ላይ ማንም ዞር ብሎ አያየኝም፣ ትኩረት የተነፈግሁና እስከመቼም የተረሳሁ ሆኛለሁ። ምንም እንኳ ዛሬ በምክርዎ እንዲረዱኝ ወደዚህ ብመጣም በመኖሬ አንዳችም የማልፈይድና አላስፈላጊ እንደሆንኩ ይሰማኛል። ለምን?" በማለት ጠየቃቸው። መነኩሴው "ልጄ አረፍ በልና እንዳማክራቸው የሚጠብቁኝን ሰዎች አነጋግሬ እስክጨርስ ጠብቀኝ" በማለት ወደ እንግዶቻቸው ሄዱ።

የቤተ መቅደሱ አትክልት ስፍራ ውስጥ ተቀምጦ ዙሪያ ገቡን የሚያስተውለው ሳሙራይ ቀኑ እስኪገባደድ እዛው ነበር። መነኩሴው ከወዲያ ወዲህ እየተንቀሳቀሱ በፍጹም ትህትናና አክብሮት ከሰዎች ጋር የሚያደርጉት ውይይት፣ የሚታይባቸው ብሩህ ፈገግታና አንድ አይነት አባታዊ ፍቅር እጅጉን አስደንቆት በትኩረት ሲያስተውላቸው ቆየ።

መሸትሸት ሲል፣ ባለ ጉዳዩ ሁሉ ሄዶ ግቢው ጭር ማለት እንደጀመረ፤ መነኩሴው ወደ ሳሙራይ ቀረቡና "አሁን ሁሉንም ነገር በጥሞና የምንነጋገርበት ሰአት ነው" በማለት ወደ ክፍላቸው እንዲገባ ጋበዙት ። ዙርያው በሚያምር የእንጨት ቅርጽ ተዋቅሮ ቁልቁል ሃይቁን ለማየት በሚያመች ጠርዝ ላይ ያረፈው በረንዳ በሙሉዋ ጨረቃ ብርሃን ደምቋል። የጠራው ሰማይ፣ የሚያብረቀርቀው ውሃና አካባቢው ላይ ያረበበው ፀጥታ፤ ስሜትን ሰቅዞ የመያዝ አንዳች ኃይል ነበረው።

"ጨረቃዋ ትታይሃለች?" በማለት መነኩሴው ዝምታውን ገረሰሱት። "እስቲ ጨረቃዋን ተመልከታት እንዴት እንዴት ታምራለች!። ከዳር እዳር ሰማዩን ያጥለቀለቀው ብርሃኗ፣ ወደ ምድር ወርዶና ውሃው ላይ ተረጭቶ የፈጠረውን ውበት አስተውል። ግን እስኪነጋ አትቆይም። የነገውን ጠዋት በተለመደው ብርሃኗ ለማብሰር ፀሃይ ትወጣለች። ፀሃይ ደግሞ ከማንም በላይ ደማቅ ብርሃን በማመንጨትና ከቅርብ እስከ ሩቅ ጥርት አድርገን እንድናይ በማስቻል የሚያክላት የለም። የተፈጥሮ ውበት፣ የተራራና ሸለቆዎች አቀማመጥ፣ የባህርና የወንዞች አፈጣጠር፣ የሰማይና የደመና አካሄድ . . . ወዘተ።"

"እኔ ሁለቱንም ክስተቶች ለአመታት ታዝቤአለሁ፣ በጥልቀትም ተከታትያለሁ። ግን አንድም ጊዜ ጨረቃ ስታማርር አልሰማሁም፣ ምንም ጊዜ ስለምን እንደ ፀሃይ ማንፀባረቅ አልቻልኩም አላለችም! ተንቄአለሁ፣ ዝቅተኝነት ተሰምቶኛል . . . ወዘተ የሚሉ ቃላት ከአፏ አልወጡም።"

"ተገቢ አይደለም!" ሳሙራይ በጩኸት አቋረጣቸው። "አባቴ ተገቢ አይደለም። ጨረቃና ፀሃይ የተለያዩ ናቸው፣ ሁለቱም የየራሳቸው የሆነ ውበት አላቸው። በምንም አይገናኙም፣ በፍጹም ሁለቱን ማወዳደር አይችሉም" አለ ድምጹን ከፍ አድርጎ።

መነኩሴው ፈገግ እንዳሉ ተነሱ። "ትክክል ነህ፣ መልሱን ራስህ አግኝተኸዋል" በማለት ወደ ፊት ተራመዱና የበረንዳውን መከለያ ተደግፈው አይናቸውን ባሕሩ ላይ እንደተከሉ ቀጠሉ "... ትክክል ነህ እኛ ሁለት የተለያየን ህዝቦች ነን። አንዱ በራሱ መንገድ፣ ብሄቱ እንደመራውና ባመነበት መስከ አለማችን የተሻለች እንድትሆን በይቻላል መርህ ጋሬጣውን ከመንገዱ ለማጽዳት ይታትራል። ለፍትህ ለርትእና ለህዝቦች ደህንነት ዘብ በመቆም ይማስናል። የተቀሩት ደግሞ የኩሬው ነፀብራቆች ናቸው። (የወጋገኑ ተራማጆች፣ የፈለጉ ተከታዮችና የድካሙ በረከቶች . . .)። ሲጀመር አንተ የታጨኸው ለመጀመርያው ነው፣ እነሆ ተወጥተኸዋል፣ በክብር ፈጽመኸዋልና የሚያሳፍርህ አንዳችም ነገር የለም"።

በማለት መልሱን አብራሩለት። ሳሙራይ ቀና ብሎ ሰማዩን አስተዋለ . . . ደስ የሚል ብርሃን . . . ሲነጋ ደግሞ በበለጠ ይደምቃል። ያሳለፈው ዘመን፣ የደከመላት ሃገርና የቆመላቸው ምስኪኖች በደማቁ ብርሃን ውስጥ እጅብ ብለው በኩራት ሲራመዱ አየና ደስ አለው። በአንድ ቃል አበጀህ . . . አበጀህ . . . አበጀህ . . . የሚሉት መሰለውና ፈገግ እንዳለ ተነስቶ ቆመ። ከዚህ በላይ ምን አለ ?።

ምንጭ ፡ **www.All Time Short Stories.com**

መነሻ ሃሳብ "Shine in your own way" * መስከረም - 2009 * አዳማ



ሶቅራጥስ

## "ፈተናው"

(ከ ክ. ል. በፊት ከ 469 - 399) የጥንታዊቷ ግሪክ ታላቅ ፈላስፋና በርካታ ቁም ነገሮችን ለአለም ያበረከተው ስመ ጥር ምሁር - ሶቅራጥስ፤ ከእለታት አንድ ቀን በመንገድ ላይ ሲሄድ ሳለ አንድ ሰው ያገኘውና እንዲህ ሲል ያናግረዋል . . .

"ይገርማል! ስለጓደኛህ ምን እንደሰማሁ ታውቃለህ? " ይለዋል።

ሶቅራጥስም "ይቅርታ - ለደቂቃ ታገሰኝ? - ማንኛውንም ነገር ለኔ ከመንገርህ በፊት ሶስትዮሽ የማጣርያ ፈተና የተባለውን ትንሽ ሙከራ ማለፍ ይጠበቅብሃል" በማለት ነገረው።

ሰውየውም " ሶስትዮሽ ማጣርያ ነው ያልከኝ? " በማለት እንዳልተረዳው ሲገልጽለት።

"አዎን - ትክክል ነህ። ከአንተ ስለጓደኛዬ ከመስማቴ በፊት ጥቂት ደቂቃዎችን ወስጄ ምን ልትነግረኝ እንደፈለክ ለመረዳት ሶስትዮሽ ማጣርያ የሚል ስያሜ የሰጠሁት ፈተና ጠቃሚ መመዘኛ ነው የሚል እምነት አለኝ" ። አለውና በቀጥታ ጥያቄውን ጀመረ።

ሶቅራጥስ - "የመጀመሪያው ማጣርያ እውነታ ይባላል። አሁን ልትነግረኝ የፈለከው ነገር በእርግጠኝነት የደረስክበት እውነት ነው?"።

ሰውየው - "አይደለም - በትክክል ስለሱ ከሰዎች የሰማሁት እና . . . "

"በጣም ጥሩ" አለው ሶቅራጥስ "እውነት ወይም ሃሰት ስለመሆኑ እርግጠኛ አይደለህም።" ወደሚቀጥለው ማጣርያ እንለፍ -

"ሁለተኛው ማጣርያ የጥሩነት ማጣርያ ይባላል። ስለጓደኛዬ ልትነግረኝ የፈለከው ጥሩ ነገር ነው?።

ሰውየው - "አይደለም - ተቃራኒው ነው" በማለት መለሰለት።

"እና" ሶቅራጥስ ቀጠለ "ልትነግረኝ የፈለከው ነገር ስለሱ መጥፎ፣ ግን እውነት ስለመሆኑ ያላረጋገጥከው ነው። ፈተናውን ለማጠናቀቅ ቀሪውን አንድ ማጣርያ ማለፍ ይጠበቅብሃል።"

"ሦስተኛውና የመጨረሻው ማጣርያ የጠቃሚነት ማጣርያ ይባላል። ይህ ስለጓደኛዬ ልትነግረኝ የፈለከው ነገር ለኔ ምን ይጠቅመኛል ብለህ ታስባለህ?።"

ሰውየው - "ምንም . . . እርግጠኛ አደለሁም።

"እሺ . . . ይሁን" አለ፤ ሶቅራጥስ በማጠቃለያው ።

"ልትነግረኝ የፈለከው ነገር - እውነት ያልሆነ፣ ጥሩ ወይም በጎ ጎን የሌለው፣ ለኔ ምንም የማይጠቅመኝ ከሆነ ከጅምሩ ለምን ትነግረኛለህ?" በማለት ከነ አሉባልታው ካጠገቡ እንዲርቅ አደረገው። ይባላል።

"ውሸት አባት የለውም" ወይም "ሀሜት ሥር የለውም" ይባላል። የሰማነውን ሰምተን (መቼም አልሰማም ማለት ያስቸግራል) አንድ እርምጃ ገብተን ብናጣራ ብዙ ጉድ እንመዛለን፣ ያፈጠጠ ፈጠራ፣ የለየለት ሃሰት አልያም እጥፍ ድርብ ግነት አያጣውም። ሃሜት፣ እውሸትና ወሬ የአንድ እናት ልጆች ናቸው፣ አንዱ ካለ አንዱ አይሆንለትም፣ ዞረው ይፈላለጋሉ፣ በአንድ ላይ ይኖራሉ። እንደማይድን በሽታ ናቸው፣ ከተጣቡ በዋዛ የማይለቁና ቀልብ ነስተው፣ ምርኮኛ አድርገው የሚያኖሩ ናቸው። ወሬኛ፣ ሃሜተኛና ውሽታም ሰዎች ደግሞ ቋሚ ማደርያና መጠለያቸው ናቸው።

በተለይ አሁን አሁን ሃሰት አሳፋሪነቱን አውልቆ አስከባሪነቱን በተከናነበበት፣ ቅጥፈት አጎንቁሎ በገዘፈበትና በአደባባይ መዋሸት ከምንም በማይቆጠርበት ጊዜ የሶቅራጥስ ሶስትዮሽ የአሉባልታ ማጣርያ እጅግ ታስፈልገናለች። እንክርዳዱን ከስንዴ፣ ገለባውን ከፍሬ፣ እውነቱን ከሃሰት፣ ሃቁን ከፈጠራ፣ ሃሜቱን ከምክር . . . ወዘተ መለያ። እስቲ ሁላችንም እንደ ሶቅራጥስ ከመስማታችን በፊት እናጣራ በውጤቱ ወሬኛን ከነእውሸቱ እርቃኑን ቆሞ እናገኘዋለን።

<u>ሶስትዮሽ ማጣርያ</u>




ምንጭ - Roger Darlington "72 Useful Moral Stories Collection" “The Socratic Triple Filter Test for Gossip” *
ጥቅምት - 2008 ዓ.ም.




## "ለውጥ"

ማየት የተሳናቸው አዛውንት የህንፃው መግቢያ ደረጃ ላይ ተቀምጠዋል። አሮጌ ባርኔጣቸው እግራቸው ላይ እንደተገለበጠ ውስጡ ጥቂት ሽርፍራፊ ሳንቲሞች ይታያሉ። ደረጃውን አስደግፈው ያስቀመጡት የካርቶን ሠሌዳ "ዓይነ-ሥውር ነኝ እባካችሁ እርዱኝ" የሚል ጽሁፍ ጎላ ባለ ቀለም ተጽፎበታል።

ለረጅም ጊዜ የህንፃው ነዋሪ የሆነው ጋዜጠኛ ጠዋት ወደ ሥራ ለመሄድ ደረጃውን ሲወርድ ዓይነ-ሥውሩ አዛውንት የዘወትር ቦታቸው ላይ ነበሩ፣ ባርኔጣው ውስጥ ያሉትን ጥቂት ሳንቲሞች በሃዘኔታ አየት አደረጋቸውና ከኪሱ አውጥቶ ጨመረባቸው። ወዲያው አንድ ሃሳብ ብልጭ አለለት።

ወደ አዛውንቱ ተጠጋ፣ ፍቃዳቸውን ሳይጠይቅ ካርቶኑን ሠሌዳ ብድግ አድርጎ በጀርባው በኩል ሌላ ማስታወቅያ በመፃፍ በዝግታ ከነበረበት መልሶ መንገዱን ቀጠለ።

ረፋድ ላይ ጋዜጠኛው ወደ ቤቱ ሲመለስ የዓይነ-ሥውሩ ባርኔጣ በበርካታ ሳንቲሞችና በተለያዩ የብር ኖቶች ተሞልቷል። ከአረማመዱ የተጠራጠሩት አዛውንት ጉሮሯቸውን ጠራረጉና "እ. . . እ እንደምን ዋልክ ልጄ? ዛሬ ጠዋት የመፀወትከኝና እዚች ሠሌዳ ላይ ጽፈህ የሄድከው አንተ ከሆንክ እባክህ ጽሁፍህ ምን እንደሚል ልትነግረኝ ትችላለህ?" በማለት ጠየቁት።

ጋዜጠኛው ፈገግ ብሎ "አባቴ . . እኔ የእርስዎን ማስታወቅያ በሌላ መንገድ ፃፍኩት እንጂ ሌላ ያደረኩት የለም" ሲል መልሶላቸው ወደ ህንፃው ገባ። ዓይነ-ሥውሩ የተቀየረውን ማስታወቅያ ለጊዜው አላወቁትም። ጽሁፉ ግን . . .
"ዛሬ ፀደይ ገባ እኔ ግን ላየው አልታደልኩም" የሚል ነበር።

የልመናውን ነገር ትተን ከእኒህ ማየት የተሳናቸው አዛውንት ገጠመኝ የምንማረው ሁላችንም በተሰማራንበት መስክ ባይሳካልን ወይም ፈቅ የማይል ውጤት ቢሆንብን፤ እቅዶቻችንን፣ የአሰራር ዘዴአችንን፣ የአገላለጽ ብልሃታችንን እና ባህሪያችንን ሳይቀር እንደሁኔታው መቀያየር፣ መለወጥና ማሻሻል ለበለጠ ግብ ያሚያበቃን . . . የስኬት ድልድይ መሆኑን በቀላሉ ያመላከተ ነው።

የኑሮ ፈተናን ይታገሉታል እንጂ አይሟገቱትም !

ደራሲ፡ ያልታወቀ
ምንጭ፡ ማሕበራዊ ድረ ገጽ - የሥነ ምግባር ጽሁፎች ስብስብ
መጋቢት - 2006 *** አዲስ አበባ

## አውሎ ነፋሱ . . . .



ከአመታት በፊት ነው። አትላንቲክ ውቅያኖስ ጥግ ከ ሳልቫዶር ከተማ በስተደቡብ ወጣ ብላ በምትገኘኝ ውሃ ገብ ምድር ላይ ኑሮውን የመሰረተው ገበሬ አዝመራውን እያስተዋለ ትክዝ ብሎ ቆሟል። የዘንድሮው ሰብል አያያዙ የሚያስደስት ቢሆንም የእርሱ ስጋት ግን ሌላ ነበር፣ የሚያግዘው ሌላ እጅ ማግኘት።

በከተማዋ ጋዜጦች ላይ ጥሩ ደምዎዝ ከሚያጓጓ ጉርሻ ጋር አክሎበት ያወጣው ተደጋጋሚ የሥራ ፈላጊዎች ማስታዎቅያ ምንም አልፈየደም። ጥምልምሉን ማእበል ተከትሎ ከውቅያኖሱ በመነሳት ምድሪቱን ቀውጢ አድርጎ ያገኘውን እያደባየ የሚያልፈውን አውሎ ነፋስ ሁሉም ፈርቶታል። በዚህ የአትላንቲክ ሰርጥ ምንም ያህል ቢከፈል ደፍሮ ወደ ገበሬው መስክ የሚመጣ ሠራተኛ ሳይገኝ ብዙ ጊዜ ቆየ።

በእርግጥ ጥቂት አመልካቾች ለቃለ ምልልስ ቀርበው የነበረ ቢሆንም የሥራውን ዝርዝር መረጃ ካዳመጡ በኋላ የሁሉም መልስ ፊታቸውን እንዳኮሳተሩ ክፍሉን ለቆ መውጣት ነበር። ይህ በእንዲህ እንዳለ ገበሬው ተስፋ በቆረጠበት ሰአት፤ አንድ መካከለኛ እድሜ ላይ የሚገኝ አጭር ከሲታ ሰው የግቢውን በር አልፎ ወደ ውስጥ ሲገባ ተመለከተ። የሰውነት አቋሙ ባያስደስተውም ካለበት አጣዳፊ ችግር የተነሳ እስቲ ልሞክረው በሚል እሳቤ ወደ እርሱ እንዲመጣ ጠራው።

"ወዳጄ እንኳን ደህና መጣህ! በግብርናው ዘርፍ የቀሰምከው እውቀት ወይም በእንደዚህ አይነት እርሻ ላይ የመሥራት ልምድ አለህን?" በማለት ተከታታይ ጥያቄዎችን ሰነዘረለት።

ሰውየው "ጌታየ - እኔ በቂ ልምድና ችሎታ አይኖረኝ ይሆናል ነገር ግን አውሎ ነፋሱ ሲያይል እንቅልፌን መተኛት እችላለሁ" በማለት በአጭሩ መለሰለት።

በመልሱ ግራ የተጋባው ገበሬ ሌላ ማብራርያ በመጠየቅ ዳግም ተስፋ አስቆራጭ መልስ ማዳመጥ አልፈለገም፣ ስለዚህ ምንም ሳያመነታ ከሲታውን ሰው በረዳትነት ቀጠረው። ቀጭኑ ሰው ታታሪነቱ አስገራሚ ነበር፣ ወፍ ሳይጮህ ይነሳል እስከ ምሽት ይሰራል። ብርታቱ ጥንካሬውና የእርሻ ሥራ እውቀቱ ገበሬውን ከማስደነቅ አልፎ በእጅጉ አርከቶታል። በዚህ አይነት ተስማምተው ሥራቸውን እየተጋገዙ በመሥራት ከረሙ።

አንድ ቀን ማታ ውድቅት ላይ አስደንጋጭ ድምጽ ገበሬውን ከእንቅልፉ ቀሰቀሰው። ባሻገር ጨለማ የዋጠውን ውቅያኖስ ከላይ ታች እየናጠ ወደ ረባዳው ሸለቆ የሚገሰግሰው አውሎ ነፋስ ምስሉም ድምጹም ያብረከርካል። ከአልጋው ላይ ዘሎ ተነሳ፣ አጠገቡ የነበረውን ፋኖስ አፈፍ አደረገና ወደ ረዳቱ ክፍል ሮጠ። ሥሙን እየጠራ በሩን በኃይል አንኳኳ፣ መልስ ሲያጣ ፋኖሱን አስቀምጦ በሁለት እጁ በሩን ደበደበ፣ ምንም የለም። በሁኔታው የተበሳጨው ገበሬ እጀታውን በኃይል ጠምዝዞ ሲገፋው ወለል ብሎ ተከፈተ።

ክፍሉ ውስጥ ገብቶ የቀጭኑን ሰው ትከሻ እየነቀነቀ ይጮህበት ጀመር . . . ። "ተነስ! ንቃ! ተነስ! አውሎ ንፋሱ መጥቷል፣ ሁሉንም ነገር ሊያጠፋ ነው፣ ሳይደርስብን መዘጋጀት አለብን፣ ሁሉንም መሸፈን አለብን" እያለ ወተወተ። ረዳቱ ሰው ፀጥ ብሎ የእንቅልፉን አጋማሽ ይለጥጣል።

የገበሬው ቁጣ ጨመረ "የተቀጠርከው ለምን መሰለህ? ተነስ ! ሥራህን ሥራ!" እያለ ሲጮህ ቀጭኑ ረዳት ወደ አንድ ጎኑ ገልበጥ አለና አይኖቹን እያሻሸ . . . "አልነሳም ጌታዬ! አልነሳም! እንደነገርኩህ አውሎ ነፋሱ ሲያይል እኔ እንቅልፌን እተኛለሁ" አለውና ተከናንቦ የተቋረጠ እንቅልፉን ቀጠለ።

ገበሬው በመልሱ ክፉኛ ተበሳጨና በዚያች ቅጽበት ሊያሰናብተው ወሰነ። "አዝናለሁ በዚህ አይነት መቀጠል አንችልም! ከነገ ጀምሮ እዚህ የምትሰራው ሥራ የለም፣ ተሰናብተሃል" ብሎት አጣዳፊውን ጉዳይ ራሱ ሊከውን በፍጥነት ወጣ። በመጀመርያ ወደ ከብቶቹ መኖ አመራ . . . የድርቆሹ ክምር በጥሩ ሁኔታ በፕላስቲክ ተሸፍኗል፣ ደርቆ ያልተወቃው ሰብልም ቅንጣት ውኃ በማያሳልፍ ሁኔታ በጥንቃቄ ተጠቅልሏል። የበሬዎቹና የላሞቹ ጋጣዎች፣ የበጎቹና የፍየሎቹ ጉሮኖዎች እንዲሁም የዶሮዎቹ ቆጦችና ማደርያ ቤቶች ሳይቀሩ መስኮቶቻቸው ተሸጉረዋል፣ በሮቻቸውም በሚገባ ተቆልፈዋል። አውሎ ነፋሱ ሊጎዳው ቀርቶ ሊነካው የሚችል አንዳችም ነገር የለም፣ ሁሉም በሚያስደንቅ ብቃት ተዘጋጅቷል። ገበሬው ውሽንንፍሩ መሃል አፉን ከፍቶ በአድናቆት እንደፈዘዘ . . . ለደቂቃዎች ያህል ቆመ።

ያኔ . . . ስለረዳቱ ጠንካራ እጆች ገባው፣ ያኔ ስለ ከሲታው ሰው ብቃት አወቀ፣ ያኔ ስለቀጠረው ሰው ማንነት ተረዳ። አውሎ ነፋሱ ሲያይል እንቅልፉን የመተኛቱ ምስጢርም ተገለፀለት፤ እርሱም መተኛት አማረው። ወዲያው ወደ ቤቱ ገባና ጥቅልል ብሎ ተኛ፣ ማእበሉ ሲያይል ጭልጥ ያለ እንቅልፍ ወሰደው። መርፈዱም አልታወቀው ከእንቅልፉ ሲነቃ የባለቅመም ሻይና የእንቁላል ጥብስ ሽታ ክፍሉን አውዶታል። ቀና ብሎ እንደተቀመጠ ቀጭኑ ሰው ቁርስ አሰናድቶ ሊቀሰቅሰው ሲመጣ አየውና እየሳቀ ተነስቶ አቀፈው . . . ቀጭኑ ረዳትም ሳቁ የተጋባበት ይመስል ተንከተከተ።

የተረጋገጠ መንፈሳዊ ጥንካሬ፣ በእውነት ላይ የተመሰረተ አእምሯዊ ብቃትና አካላዊ ዝግጅት . . . ከፍርሃትና ካላስፈላጊ ስጋት ፍጹም ነፃ ያደርጉናል። ቀጭኑ ረዳት አውሎ ነፋስ እንደሚመጣ አውቋል፣ ቢመጣም ባይመጣም ደግሞ የሚያስጨንቀው ጉዳይ የለም። የተጠና ቅድመ ዝግጅት ወይም አስተማማኝ ብቃት ይሏችኋል ይህ ነው። ሁላችንም እንደ ቀጭኑ ረዳት መብሰል ላያስፈልገን ይችላል፣ የረዳት አመራረጣችንና ተገቢውን ሰው የማግኘታችን ነገር ግን እንደገበሬው ሁሌ ስለማይቀና ችግሮቻችንን ውስብስብና ዘርፈ ብዙ ሲያደርግብን ኖሯል . . . ምን ኖሯል ብቻ አሁንም እንዳለ ነው። ረዳቶቻችን ከኛ የማይሻሉ ይሆኑና አልያም ከአንድ ባህር የተቀዳን በመሆናችን አምናም፣ ዘንድሮም ለከርሞም እንደ ድመቷ "ሽህ ቢታለብ ያው በገሌ" ይሆንብናል። አለፍ ሲል ደግሞ ረዳቶቻችን ከኛም የባሱ ዱልዱሞች፣ ከእውቀቱ በጅምር፣ ከብቃቱም በስንዝር ይሆኑና "ጮሃ የማታውቅ ወፍ ስትጮህ እለቁ እለቁ ትላለች" እንደሚባለው ተረት መዝሙራቸው - ተጠንቀቁ፣ ፉጨታቸው - ልቀቁ፣ ሁለመናቸው - እለቁና . . . ወዘተ ቁና ቁና እርግማን እያዘነቡ የሚያሳቅቁ ይሆኑብናል። የረዳት ነገር፣ የአማካሪና የአጋዥ ነገር የዋዛ አይደለም። ለልማትም ለጥፋትም ከሚነገርለት በላይ እጅግ ወሳኝ ጉዳይ ነው። መሬት ለወረደ ስኬት ዋናው መሰረት የአስፈፃሚው ብቃት ስለመሆኑ መጠራጠር አያስፈልግም። የረዳት ጉዳዮች ሚንስትር ያልተሾመልን ሁሉንም ሆኖ በሁሉም ውስጥ የሚኖር፣ የወል ሥም ስለሆነም ይመስለኛል።

ወዳጆቼ ጥሩ ጥሩ ተረቶች አሉን "ጥንት ነበር እንጂ መጥኖ መደቆስ ፡ አሁን ምን ያደርጋል ድስት ጥዶ ማልቀስ" አንድ በሉ "ሰርገኛ መጣ በርበሬ ቀንጥሱ" ሁለት በሉልኝ . . . ሌሎችም ብዙ ብዙ ያልተማርንባቸው ተረቶች አሉን። እኛም እነሱም አልተቀየርንም። እንደውም የባሰብን ይመስለኛል። አሁን ላይ የኛ ቀርቶ ተረቶቹ ቢሻሻሉ የሚመጥነን "ድስት ጥዶ ማልቀስ ሳይሆን" "ድስት ሳይኖር ማልቀስ" "በርበሬ ቀንጥሱ" ሳይሆን "በርበሬ ትከሉ" የሚለው ይሆናል። ለእዚህ ነው በየአመቱ ተመሳሳይ ጎርፍ፣ በየአመቱ አንድ አይነት ቸነፈር፣ በየጊዜው የማይነጣጠሉ የችግር አይነቶች የሚጎበኙን።

እንደ ገበሬው አይነት ረዳት ማግኘት መታደል ነው። ሰብሉን በሚገባ ሸክፎ፣ ዙርያ ገባውን በአስተማማኝ ጠርንፎ ሲያበቃ አውሎ ነፋሱ ሲያይል እንቅልፉን የሚለጥጥ ጀግና። አውሎ ነፋሱ እንደፈለገው እያበደ ቢመጣ አውድማውን ለበነጋው ውቅያ አጽድቶ ከመሄድ ውጭ ምን ያገኛል? ምንም። አንዳንዶቻችን ዝናብ ሲጥል አልጋችን ውስጥ ገብተን ለጥ ብለን መተኛት ደስ ይለናል - አይደል?። ልብ በሉ ምኞት ብቻ ነው። እንደተባለው ዶፉ ሲወርድ እንተኛለን - ከውጪ ግን የተሰጣ ልብስ ትተናል ወይም በሌላው አቅጣጫ ጣርያችን ያፈሳል፣ እህታችን ቤቷ አልደረሰችም፣ ወንድማችን ከናካቴው መጠለያ የለውም፣ ጎረቤታችን ዝናብ የመፍራት በሽታ ስላለበት በጭንቀት ይርዳል፣ ስለመዝነቡ የማያውቁና የሳር ጎጇቸውን ለመሸፈን በመጣደፍ ላይ ያሉ በርካታ ብጤዎቻችን ሞልተዋል "የነቶሎ ቶሎ ቶሎ ቤት ምንትሱ ሰንበሌጥ" ይባላል ሰንበሌጡም እኮ በደህና ቀን አጭደው ካኖሩት ነው አልያ ከየት ይገኛል? ባዶ መቅረቱ ነው። በዚህ ሁኔታ የሚዘንበው ዝናብ ደስ ብሎን - ጥቅልል ብለን ከተኛን እውነትም . . . ጠንቶብናል እንጂ ሌላ ምን ይባላል።

ነገን አስበን ስለማንቆጥብ ጥንቧም ጉዳት ታይልብናለች፣ ሥራ እያለን ስለማንዘጋጅ ጡረታችን ሲኦል ይሆንብናል፣ በጊዜ ያላዳበርነው እውቀት ውሎ አድሮ ሲገደን፣ በደህና ቀን ያላኖርነው ጥሪት እንደ ፍየል ጭራ ሲያጥረን፣ ያላቆየነው ወዳጅነት፣ ያላዳበርነው አንድነት፣ ያላፀናነው ፍቅር . . . ወዘተ ባለቀ ሰአት ከየት ይመጣል። ሁላችንም በየጉዳያችን ላይ ቅድመ መከላከከልና የተሟላ ጥንቃቄ ስለማናደርግ፣ በአጠቃላይ በብቃት ስለማንዘጋጅ ለችግር እንደተጋለጥን አለን። ወዳጆቼ ዋናው ቁልፍ ነገር ጥረታችን ከአምላክ ፈቃድ የተነጠለ፣ ሁለመና ውጥናችን ለፈጣሪ አምላክ ያልታመነ ከሆነ ግን ድቅድቁን ጨለማና ሃያሉን አውሎ ነፋስ የሚያሻግረው እጅ አይታየንም፣ ካላየነው ደግሞ አንይዘውም፣ ካልያዝነው ደግም አንወጣም፤ እዛው ነን "ምን ተይዞ ጉዞ"። ብቃቱን የሚለግሰንም ልብ ያለው ረዳት . . . የሚሰጠንም እርሱ ብቻ ነው ። እርሱው ይርዳን - አሜን ።

ምንጭ፡ www.moralstories.org All Time Short Stories - "When the wind blows"
ጥር 2009 ዓ.ም. አዲስ አበባ



**ማነቆ**

ሰኞ ማለዳ በመደበኛው የሥራ ሰአት የድርጅቱ ሠራተኞች በሙሉ ወደ ቅጥር ግቢው በመግባት ላይ ነበሩ። ፊት ለፊት የማስታዎቅያ ሰሌዳው ላይ አንድ ማሳሰብያ ተለጥፏል።

"ትናንትና እሁድ እለት የእድገታችሁ ማነቆ የነበረውና በድርጅቱ ውስጥ እድገት እንዳታገኙ ሲያፍን የነበረው ሰው ከዚህ ዓለም በሞት ተለይቷል ። የቀብር ሥነ ሥርአቱም ዛሬ በዘጠኝ ሰአት የሚፈፀም ሲሆን ስድስት ሰአት ላይ በትልቁ የስብሰባ አዳራሽ የስንብት መርሃ ግብር ስለተዘጋጀ እንድትገኙ እናሳስባለን" ይላል።

ሁሉም እየተሽቀዳደሙ ያነቡትና እርስ በእርስ እየተንሾካሸኩ ይመለሳሉ። በመጀመርያ ስለሞተው ባልደረባቸው ያዝናሉ፣ ወዲያው ደግሞ ስለማንነቱ ያስባሉ፣ ማነው እሱ? እንዳናድግ ማነቆ የሆነብን፣ ይሄ ምቀኛ ሰው ማን ይሆን? እያሉ በጉጉት ይጠያየቃሉ።

ከቀኑ ልክ ስድስት ሰአት ሰራተኛው በሙሉ ከአዳራሹ ፊት ለፊት ተሰልፏል። የደህንነት ሁኔታው ከወትሮው ጠበቅ ያለ ለመሆኑ በጥቁር የደንብ ልብስ አለፍ አለፍ ብለው ወደ ረጅሙ ሰልፍ በሚያተኩሩት የጥበቃ ሰራተኞች ብዛት ያስታውቃል። ከውስጥ የአዳራሹ ዙርያ ደብዘዝ ብሎ ወደ መሃከል ያለው ስፍራ በወፋፍራም ሻማዎች ብርሃን ደምቋል። ከመግቢያው ጀምሮ በቀጭኑ የተነጠፈው አረንጓዴ ስጋጃ እስከ ጥግ ተዘርግቷል። እንደ ደረጃ አጠርና ረዘም ያሉት ጠረጴዛዎች በነጫጭ አበቦች ተሸፍነው የሃዘን መግለጫ ካርዶች ተቀምጠውባቸዋል። ከወገብ በላይ መስታዎቱ የተከፈተው የአስከሬን ሳጥን በጉንጉን አበቦች እንዳሸበረቀ ከፍ ብሎ ይታያል። ትጉልጉል እያለ ሽቅብ የሚወጣው እጣን፣ ከሰንደሎቹ ጢስና ከሽቶው ጠረን ጋር ተዳምሮ አካባቢው በመልካም መአዛ ታውዷል።

መርሃ ግብሩ ተጀመረ . . . ቀስ በቀስ ወደ አዳራሹ በመግባት ለመጨረሻ ጊዜ የባልደረባቸውን አስከሬን የሚሰናበቱበት ሰአት ሲደረስ ውጥረቱ እየጨመረ መጣ። የሟቹ ማንነት በሁሉም አእምሮ ውስጥ የሚያጓጓም የሚያስፈራራም ጥያቄ ሆኗል። እርስ በእርስ "እንዴት እስካሁን ሲያቀረቁዘን ቆየ? በነገራችን ላይ ማነው እሱ? . . ." ያወራሉ። በውስጣቸው ደግሞ "እንዳላድግ ቁልቁል የያዘኝ ሰው ማን ነው? ይኸ ምቀኛ የትኛው ይሆን? ለሁሉም ግን ሞቷል! ይህም አንድ ነገር ነው" ይላሉ። ረጅሙ ሰልፍ እየተግተለተለ ወደ ውስጥ በዘለቁ ቁጥር ልቦቻቸው በፍጥነት እየደለቁ ጭንቅ ጭንቅ ይላቸው ጀመር። አንድ በአንድ ወደ ሳጥኑ ተጠግተው ቁልቁል አስከሬኑን ሲመለከቱ፤ ሰውነታቸው እየተብረከረከና ቁና ቁና እየተነፈሱ፤ ነብሳቸውን ያዩ ያህል ድርቅ ብለው ይቆማሉ። የተከፈተው ሳጥን ውስጥ ረጅም መስታዎት ተጋድሟል። በጉጉት ወደ ውስጥ የሚያተኩሩት ሠራተኞች የራሳቸው ምስል ሲያፈጥባቸው ይደነግጡና፤ እየተንገዳገዱ ይሄዳሉ። መስታወቱ ጠርዝ ላይ አንድ ጽሁፍ ተለጥፏል "እድገትህን የመወሰን ችሎታና ብቃት ያለው አንድ ሰው አለ ። እርሱም . . . **አንተ ነህ! (አንቺ ነሽ !)**" ይላል።

ትክክል ነው . . . ለሕይወትህ መሰረት የሆንከና ራስህን ለመለወጥ ኃላፊነቱን የምትወስድ ብቸኛው ሰው አንተ ነህ (አንቺ ነሽ)። እኛ . . . በእያንዳንዱ ደስታና ሃዘን፣ ስኬትና ውድቀት፣ ልማትና ጥፋት ውስጥ ቀጥታ ተሳታፊና ወሳኝ ፍጡራን . . . እኔ፣ አንቺ፣ አንተ ብቻ ነን።

ወዳጆቼ ! ራሳችንን ለመርዳትና ለማገዝ፣ ለመግባባትም ይሁን ለመከላከል፣ ለመገንባትም በሉት ለማፍረስ ተጠያቂዎቹ እኛ ብቻ ነን። የራሳችን ሕይወት እስካልተቀየረ ድረስ አለቆቻችን ቢቀየሩ፣ ጓደኞቻችን ቢቀየሩ፣ ጎረቤትና ባልደረቦቻችን ቢቀየሩ፣ ድርጅታችን ቢቀየር . . . ወዘተ እኛ ተቀይረናል አይባልም። በአስተሳሰብ መጥቀን ከአቅማችን በላይ ብንምዘገዘግ፤ አልያም ከደረጃችን በመውረድ አዘቅዝቀን ብንገኝ ለሁሉም ነገር ተጠያቂዎቹና ኃላፊነቱንም የምንወስድ እኛ ራሳችን ብቻ ነን። መፍጠር ያለብን እጅግ አስፈላጊና ወሳኝ ግንኙነት ከራሳችን ሕሊና ጋር የምንመሰርተው ጥብቅ ዝምድና ነው። ሌላ ምንም ሰበብ አያስፈልግም።

የምንኖርባት ዓለም ልክ እንደ መስታወት ነች። የማናችንንም ወቅታዊ ጥንካሬና ድክምት ምንም ሳትሸሽግ መልሳ በማንፀባረቅ ታሳየናለች። ፍንትው ያለው የእኛና የአለም እውነታ የቀብሩ ሳጥን ውስጥ ለጥ ብሎ የተኛው መስታዎት ነው።
የሞት አፋፍ ላይ ቆሞ ቁልቁል ወደ ጉድጓዱ በማጮለቅ ለስኬትም ይሁን ለውድቀት የመጨረሻውን ተጠያቂ ማንነት መለኮታዊ በመሰለ ችሎታ ማየት፣ እናም እንዳፈጠጥንበት ፊት ለፊት ሲያፈጥብን ችለን መጋፈጥ . . . ለውጥ አያመጣም ትላላችሁ?።

እስቲ ጥቂት ስንኝ ለእኛ - ለባለታሪኮቹ . . .

**<u>እኛው ነን !</u>**

እጅ የሚያስነሳ ቀላጤ - የሚያስጎነብስ በሌለበት
እንደው በባዶ ሜዳ - አቀርቅረን ስንሰነብት
ሳንገደድ አደግድገን - ላንመረቅ እጅ ነስተን
የራሳችን እንቅፋቶች - ከቶ ሰበብ ማያልቅብን
አንተ ነህ - እኔ ነኝ - አንቺ ነሽ - እኛ ነን ።

ሳንሞክር ሳንለፋ - ታግለን ሳንጣጣር
የችግርን ቀምበር - አጥልቀን ስንፎክር
ቀና ማለት ገዶን - ጎብጠን እንደቀረን
ወዛሙ ሳጥን ውስጥ - ገብተን የተጋደምን
እኔ ነኝ - አንተ ነህ - አንቺ ነሽ - እኛ ነን ።

በራሳችን ጥፋት - ሌሎችን ስንወቅስ
በራሳችን ጉድለት - ሌላውን ስንጠቅስ
እንደው በንቶ ፈንቶ - ከላይ ታች ስንባዝን
ቁርጡ ቀን ተዳርሶ - ሳንሞት ያበቃልን
እኔ ነኝ - አንቺ ነሽ - አንተ ነህ - እኛው ነን ።

ሰበብ ስናበዛ - እዚም እዚያም ስንል
መወሰን አቅቶን - ስንባክን ስንዋልል
የተንዛዛው ጊዜ - የባከነው ምክር
ተንጠፍጥፎ ሳያልቅ - ዳግም እንሞክር

ሳጥኑ ተከድኖ - ሰንዱቁ ተዘግቶ - ሳይቆለፍበት
መዝጊያው ተቀርቅሮ - ዙርያ ገቡ ጠብቆ - ሳይታሸግበት
ምስማር ሳይመታ - ጭራሽ ሳይደፈን - ቀዳዳው ሳይጠፋ
በቅንጣት ስንዘራ - በንጥፍጣፊ ኃይል - እንጣር በተስፋ

 Moral Stories.com - life page – <u>"Looking at Mirror"</u>
መጋቢት 2009 ዓ.ም.



## "ሰባራው እንስራ"

ቻይናውያን ውሃ የሚቀዱበት የሸክላ እንስራ ከእኛው ጋር ተመሳሳይ ሲሆን የሚያጓጉዙበት ዘዴ ግን ለየት ያለ ነው። አንድ ረጅም የእንጨት ዘንግ በመጠቀም በገመድ የታሰሩ ሁለት ተመጣጣኝ እንስራዎችን የዘንጉ ዳርና ዳር ላይ ያንጠለጥሉና መሃከሉን ትከሻቸው ለይ በማድረግ ይሸከሚቸዋል። ቻይናዊው ገበሬ የሚያከናውነውም ይህንኑ ከአያት ቅድም አያቶቹ ሲያያዝ የመጣውን አሰራር ነበር።

በየቀኑ ጠዋትና ደንገዝገዝ ሲል ወደ ጅረቱ ይወርድና ሁለቱንም ትልልቅ እንስራዎች እኩል ውሃ ሞልቶ በመሸከም፤ ረጅሙን አቀበታማ መንገድ በዝግታ ተጉዞ ወደ ቤቱ ይመለሳል። አንደኛው እንስራ ምንም እንከን የሌለበትና ትክክለኛ ሲሆን ሌላኛው ግን ስንጥቅ አለው። በዚህ ምክንያት በሰባራው በኩል ውሃ ስለሚያፈስ ያንን ሁሉ አቋርጦ እቤት የሚደርሰው ከግማሽ ያነሰ ነበር።

ይህ ድርጊት አንዴም ሳይቋረጥ ለአራት አመታት ያህል ቀጠለ፣ ገበሬው ማለዳና ምሽት ወደ ወንዝ ይወርዳል አንድ እንስራ ተእኩል ውሃ ቀድቶ ይመለሳል። በዚህ ሁኔታ ደህነኛው እንስራ በእጅጉ ይደሰታል "ለተሰራሁበት አላማ ትክክለኛውን አገልግሎት የምሰጥ፣ ጠንካራና እምነት የሚጣልብኝ እኔ ብቻ ነኝ" በማለት ይኩራራል . . . ይፎክራል። ሰባራው ግን ያፍራል፣ ከተሞላው ውሃ ግማሹን ብቻ በማድረሱ ራሱን ይኮንናል፣ በየጊዜው ወንዝ ወርደው በተመለሱ ቁጥር በፀፀት ይሸማቀቃል . . . በዚህ አይነት የሚያደርገው ጠፍቶት የሆዱን በሸክላ ሆዱ እንደያዘ ለረጅም ጊዜ ታገሰ።

ከአራት ዓመታት በኋላ ምሬቱ ቢበዛና ትእግስቱም መዳረሻውን ቢያልፍ ገበሬውን ለማነጋገር ወሰነ። አንድ ብራ ምሽት ከወንዙ ጥጋት ላይ አረፍ እንዳሉ እንደዚህ በማለት ጀመረ . . . "እኔ በጣም አፍሬአለሁ፣ በምታየውና በዚህ ጎኔ ላይ ባለው ስንጥቅ ምክንያት የሞላኸኝን ውሃ ሜዳ ለሜዳ እየረጨሁ የማደርሰው ግማሹን ብቻ ነው፣ ቀና ብየ አይንህን ማየት እንኳ አልቻልኩም፣ በጣም ተጨንቄአለሁ . . . የሚጠበቅብኝን አለመፈፀም፣ ሃላፊነቴን አለመወጣትና አይሁኑ መሆን ውርደት ነው! . . . ተዋርጃለሁ" በማለት በቁጭት እየተንቀጠቀጠ ነገረው።

ገበሬውም በጥሞና ካዳመጠው በኋላ ተመቻችቶ በመቀመጥ ያስረዳው ጀመር "ማወቅ ያለብህ ብዙ ነገሮች አሉ፣ እስቲ በቅድሚያ አንዱን ልጠይቅህ። ሁል ጊዜ ከወንዙ ስንመለስ አንተን በስተግራ ያኛውን ደግሞ በስተቀኝ በኩል ተሸክሜአችሁ እንደምጓዝ አስተውለህ ታውቃለህ?"።

"አላስተዋልኩም። ግን - አዎ . . . ልክ ነህ፤ ሁሌም በግራ ትከሻህ በኩል ነኝ"።

"እሺ . . . ስንሄድ በስተቀኛችን ስንመለስ ደግሞ በግራችን በኩል የሚውለው የአትክልትና የአበቦች መደብስ ምን ይመስልሃል?"።

"ምንም . . . ያው በጣም የሚያምርና ለምለም የእጽዋት መደብ ነው"።

"ልክ ነህ እኔ አዘጋጀሁት፤ ያደገውና ያፈራው ግን በአንተ ጥረት ነው። ስንጥቅህም የታሰበና አውቄ ያደረኩት ነው። የምታንጠባጥበው ውሃ የተዘራ እንዲፀድቅ - የበቀለው እንዲያድግና ህይወት እንዲቀጥል የሚነስነስ በረከት ነው። ከዓመት እስከ ዓመት እኔና ቤተሰቤ ጣፍጦን የምንመገበው አትክልት፣ ሳሎናችንን ያስዋቡት አበቦች ሁሉም . . . ሁሉም አንተ ዘወትር በምትለግሳቸው ንጹህ ውሃ የተገኙ ናቸው። በማያፈሰው እንስራ በኩል ምን አለ? ምንም። በእርግጥ ምንም ውሃ ጠብ ሳያደርግ ሙሉ ሙሉውን እንስራ ሲያግዝ ኖርዋል፣ ያንተ ግን ልዩ ነው፤ እጹብ ድንቅ! የሚያኮራ . . . ይልቅስ ፍጹም የማያሳፍር ተግባር ነው" በማለት ዘርዝሮ አስረዳው። ይባላል።

እንደ ሰባራው እንስራ ኃላፊነቴን ሳልወጣ ቀረሁ፣ የሚፈለግብኝን ሳላደርግ ዘገየሁ አልያም ግዳጄን ሳልፈጽም . . . ወዘተ በሚል ሰቀቃ ማፈር መፀፀትና ራስን ተጠያቂ ማድረግ የመልካም ስብእና ምልክት ነው። በራሱ እንደ ውጤት ባይቆጠርም እንከን ለማይወጣለት ስኬት የተዋጣለት ዋስትና ነው ማለት ይቻላል። ማድረግን የመሰለ ነገር የለም፣ መልካም ተግባርና በጎ ሥም ከሌላ አንደበት ሲሰማ፣ አድናቆትና ምስጋናም በሌላ ወገን ሲነገር ደስ ይላል። ስኬትና አጥጋቢ ውጤቶችም በተጨባጭ ድርጊቶች ሲረጋገጡ፤ እውነተኛውና ማስተዋል የታከለበት ደስታ ይህኛው አይነት ነው። እንደተባለው የሚያኮራ እንጂ የማያሳፍር።

በየቦታው የምናየው ግን ተቃራኒውንና ፍጹም ተቃራኒውን ነው። ቅንጣት አስተዋጽዎ ባላበረከትንበት መድረክ መሪ ተዋናይ ሆነን ቁጭ የምንል፣ ባልዋልንበት የጦር አውድማ ከኛ በላይ አርበኛ ለአሳር በሚል ፉከራ ለገላጋይ የምናስቸግርና ሙገሳን አሰፍስፈን የምንጠብቅ ደፋሮች በበረከትንበት ዘመን፤ እንደ እንስራው ኃላፊነቱን ባለመወጣቱ የሚቆጭ አልያም አደራችንን በማጓደላችን የምንፀፀት . . . እንገኝ ይሆን? በእኔ በኩል እንጃ።

ምንጭ ፡ Roger Darlington's World
"The cracked pot"
ጥቅምት 2009 ዓ.ም. - አዲስ አበባ

**የጨነቀው ባል**

ባልና ሚስቱ ከሦስት አስርታት በላይ በዘለቀ የትዳር ህይወታቸው ፍጹም ደስተኞች ናቸው። በዚህ መተሳሰብ በሰፈነበት ጎጆ ውስጥ ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ባልን የሚያስጨንቀው አንድ ጉዳይ ተከስቷል። ይኸውም ከቅርብ ጊዜ ወዲህ የውድ ባለቤቱ የመስማት ችሎታ እየቀነሰ መምጣቱ ሲሆን እንዴት እንደሚነግራትና በህክምና የምትረዳበትን ሁኔታ እንደሚያመቻች ጨንቆት ነበር።

በኋላም የቤተሰቡን ሃኪም አማከረና በቅድሚያ የመስማት ችሎታዋን መመዘን ስለሚያስፈልግ ሊጠቀም የሚገባውን ቀለል ያለ መፍትሄ ነገረው "ከባለቤትህ አርባ እርምጃዎች ያህል ራቅ በልና ድምጽህን ከፍ አድርገህ ዘወትር በምታናግራት ቅላጼ ተናገር። ከዚያም መስማት አለመስማቷን አረጋግጥና ካልሰማች ርቀትህን ወደ ሰላሳ እርምጃ ቀንስ። እንዲህ . . . እንዲህ እያደረግህ ከሃያ እርምጃ . . . ወደ አስር እርምጃ . . . ከዚያም . . . እያልክ በመቀነስ እስክትሰማህ ድረስ ቀጥል። በዚህ መንገድ የመስማት ችሎታዋን መጠን ስለምንረዳ በቀጣይ የሚያስፈልጋትን የህክምና ድጋፍ ለመወሰን ይጠቅመናል" በማለት አስረዳው።

በነጋታው ምሽት ባል ወደ ቤት ሲገባ ሚስቱ እራት እየሰራች ነበር። በዚህ አጋጣሚ የዶክተሩን ምክር ሥራ ላይ ማዋል ፈለገና ከሚስቱ አርባ እርምጃዎችን በመራቅ ጮክ ብሎ "ውዴ! ዛሬ እራታችንን ምን እየሰራሽ ነው?" በማለት ጠየቃት። ዝም፤ መልስ የለም።

እንደተባለው አስር እርምጃዎችን ቀንሶ ደገመው . . . ምንም የለም። ደነገጠ!። ሃያ እርምጃ ሲቀረው "ውዴ የዛሬው እራታችን ምንድን ነው?" ሲል ጠየቃት፤ በእርግጠኝነት አንድ ቃል እንደሚሰማ ጠብቆ ነበር፤ ነገር ግን መልስ ሲያጣ የሁኔታው አስከፊነት በጣም አስጨነቀው።

በዝግታ እየተራመደ አስር እርምጃ ሲቀረው የመጨረሻውን ሞከረ . . . ጠበቀ . . . ጠበቀ፣ ምላሽ ባለማግኘቱ ተስፋ ቆርጦ አንገቱን እንደ ደፋ ወደ ባለቤቱ ሄደና ከጀርባዋ ሆኖ አቀፋት . . . "ውዴ እራታችን ምንድነው?" በጆሮዋ ሹክ አለ።

ባለቤቱ ግን በመሰላቸት ጮኸችበት . . . "ምን ሆነሃል ጆን? ዶሮ ነው ስልህ ከዚህ ጋር ለአምስተኛ ጊዜ ነው" አለችው።

በቃ፤ ዝም አለ። ታሪኩም እዚሁ ላይ አበቃ። ምስኪን ባል ለካንስ ከፉኛ የመስማት ችግር ውስጥ የነበረው እርሱ ራሱ ነበር?።

አንዳንዴ የኛ ችግር ከሌሎች መባሉን ሳናውቅ እንጨነቃለን፣ ለገዛ ቤተሰቦቻችን፣ ጓደኞቻችን፣ ወገኖቻችን . . . ወዘተ ቀርቶ ለሌላ ለማንኛውም አካል ጥሩ ማድረግና መጨነቅ ክፋት የለውም። እንደውም የበጎ አስተሳሰብና የሰብአዊነት ምልክት ነው። የባል ጭንቀትም ይኸው ነው - መልካሙ አይነት። አስከፊው ደግሞ ችግሮችና መንስኤዎቻቸው ሁሉ ሌሎችና የሌሎች ብቻ እንደሆኑ በመደምደም ራስን ከሁሉ ነፃ አድርጎ የማሰብ አባዜ ነው። ከዚህስ ይሰውረን!።

ምንጭ : www.AllTimeShortStories.com
"CONCERNED HUSBAND"
መስከረም - 2009 * አዲስ አበባ



**"ፈለግ"**

ያኔ . . . ወጣት እያለሁ - ዓለምን የመቀየር ጽኑ ፍላጎት ነበረኝ። ውሎ ሲያድር ዓለምን መቀየር አዳጋች መሆኑን ተረዳሁ፣ እናም አገሬን ለመቀየር መጣር ጀመርኩ።

ይህም

አልተሳካ አገሬን መቀየር አልቻልኩም፣ ስለዚህ ትኩረቴን የምኖርበትን ከተማ ወደ መቀየር አዞርኩ።

ይሁን እንጂ ከተማውን የመቀየሩም ነገር አልሆነልኝም፣ ዓመታት አልፈው በሽምግልናዬ ዘመን ቤተሰቦቼን መቀየር እችላለሁ ብዬ ተነሳሁ። ከንቱ ድካም! ሙከራዬ ከጅማሮ አላለፈም።

አሁን እንዲህ ካረጀሁ በኋላ፤ አንድ ጥርት ያለ እውነታን ተገነዘብኩ፤ ይኸውም በእርግጠኝነት መቀየር የምችለው ራሴን ብቻ ነበር። ምን ያደርጋል? የተገለፀልኝ ዛሬ ነው። ገና ያኔ ወጣት እያለሁ ራሴን ቀይሬ ቢሆን ኖሮ፣ ቤተሰቦቼም ተቀይረው ቤቴ ውስጥ ትልቅ ለውጥ ማምጣት በቻልኩ ነበር። እኔና ቤተሰቤ ደግሞ ዘመድ ጓደኛና ጎረቤቶቻችንን ብሎም ማህበረሰቡን በመለወጥ ከተማችንን መቀየርና በለውጥ ጎዳና ማራመድ በተሳካልን ነበር።

መቼም ሁሉም በነበር ቀረ እንጂ፤ የከተማችን ሕዝብ ተሳትፎ ባደገና በጎለበተ መጠን በሃገር ይረጃ አርአያ በመሆን ተጽእኖ ማሳደርና መለወጥ ይቻል ነበር። ከዚያም በሂደት ሀገሬ በተጨባጭ እድገት ተቀይራ ለሌሎች የለውጥ ተምሳሌት ስትሆን . . . ያኔ - የኔ ቀዳሚ ራእይና ፍላጎትም ዓለምን በመቀየር እውን ሆኖ ይደመደም የነበረው በዚህ ወጥና ተደጋጋፊ ሂደት ብቻ መሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም። አሊያ ራስን ሳይለውጡ ዓለምን ቀርቶ ቤተሰብን ለመቀየር መሞከር ከምኞት የማይዘል ከንቱ ቅዠት ነው። ዛሬ ከመሸ ለኔ የተገለፀልኝን ሃቅ፣ እናንተ በጠዋት ተገንዝባችሁ እንደኔ ከመጨረሻው ሳይሆን ከመነሻው ትጀምሩ ዘንድ ምክሬን መለገስ ወደድሁ።

ከልብ አመሠግናለሁ !

ደራሲ፡ ሥሙ ባልታወቀ መነኩሴ - በ 1100 (ዓመተ ዓለም) ተፃፈ
ምንጭ፡ Meaningful Stories Collection pdf "I wanted to change the world"
ሚያዝያ - 2007 ዓ. ም





## "የአፍ ወለምታ"

"ራቅ ባለው ጊዜ በአንድ መንደር ውስጥ ከእናትና አባቱ ጋር የሚኖር ትንሽ ልጅ ነበር። ከእለታት በአንዱ ቀን ከቤታቸው ፊት ለፊት እየተጫወተ ሳለ እናቱ ወንዝ ወርዳ ውሃ ለመቅዳት ፈለገችና "አቡሽዬ ውሃ ቀድቼ እስክመለስ ከአጥሩ ሳትወጣ እዚሁ እየተጫወትክ ጠብቀኝ" ብላው እንሥራዋን አዝላ ወጣች።

አቡሽ ጥቂት እንደተጫወተ ወደ ግቢው በር ሄደና በትንሹ ከፈት አርጎ የውጭውን ትእይንት ማስተዋል ጀመረ። ከቀጭኑ የእግር መንገድ ባሻገር በአረንጓዴ ሳር የተሸፈነ መስክ ይታያል፣ የሚያማምሩ ቢራቢሮዎች ክንፋቸውን እያርገበገቡ ከአንዱ ወዳንዱ ይበራሉ። አቡሽ አላመነታም ይህን የማይገኝ እድል ለመጠቀም እየሮጠ ከቤት ወጣ። ትንንሽ እግሮቹ የቻሉትን ያህል እየዘለሉ መስኩን በአግድመት ሰንጥቀው ወደ መሃል ገቡ። ሲሻው እንደፍራሽ የሚመቸው ሣር ላይ እየተንከባለለ፣ ከቢራቢሮዎቹ ጋር እየተሯሯጠና ደስ በሚል የአበቦች መአዛ የታወደውን አየር እየማገ ሜዳውን አቋርጦ ትልልቅ ባለጥላ ዛፎች ከከበቡት ጫካ ደረሰ።

ዛፎቹ ብቻቸውን አልነበሩም በተለያየ ቀለም ያሸበረቁ ወፎች በነጠላና በቡድን እጅብ ብለው እዚህም እዚያም እየከነፉ በሚያሰሙት ጣእመ ዜማ አካባቢውን አድምቀውታል። አቡሽ ግቢው ውስጥ ከሚያያቸው አእዋፍ በአይነትም በብዛትም አዲስ ስለሆኑበት የበለጠ ለማየት ጓጉቶ በሩጫ ጫካው ውስጥ ገባ። ረጅም የእግር መንገድ ተጉዞ የማያውቀው ልጅ ደከመው፣ ወደ ቤቱ መመለስ ፈልጎ በእርምጃም - በሶምሶማም ቢሄድ ቢሄድ ከጫካው መውጣት አልቻለም። መንገዱ ጠፍቶበታል። አሁን ከድካሙ ሌላ ውሃ ጥምና ርሃብ ተጨምረው በቀስታ መራመዱን ቀጠለ። ጊዜው እየመሸ ሲመጣ ጨለማ የከበበውን ጫካ ፈራ። ከአንድ ዛፍ ስር ለማረፍም ወሰነና የወዳደቁት ቅጠሎች ላይ ጋደም እንዳለ ጭልጥ ያለ እንቅልፍ ወሰደው።

እኩለ ለሊት ላይ ጫካው ውስጥ ይሄድ የነበረ ትልቅ አንበሳ ልጁን አየውና ቆመ። አንበሳው ሚስቱንና ልጆቹን አዳኞች ስለገደሉበት የሚኖረው ብቻውን ነበር። ትንሹን ልጅ ሲያይ በጣም ስላሳዘነው ትቶት መሄድ አልፈለገም፣ ምንም ክፉ ነገር እንዳያገኘው አጠገቡ ተቀምጦ ሊጠብቀውና ከእንቅልፉ ሲነቃ ሊያናግረው ወስኖ ቁጭ አለ። ልጁ በርዶት ሲገላበጥ ነቃና አንበሳውን ሲያይ ደነገጠ። አንበሳው "አይዞህ እኔ የጫካው ንጉስ አንበሳ ነኝ፤ ስትነቃ ላናግርህ እየጠበኩህ ነበር እንዴት ብቻህን እዚህ ዱር ውስጥ ልትገኝ ቻልክ?" ሲል ጠየቀው።

ልጁም እንዴት እንደመጣ ሁሉንም ነገር ዘርዝሮ ነገረው። በጣም እንደራበው፣ እንደፈራና ብርዱንም እንዳልቻለው አከለበት። አንበሳውም "ና ወደ እኔ ቤት አብረን እንሂድ እዛ ያሻህን ሁሉ ታገኛለህ "አለውና ተያይዘው ሄዱ። የአንበሳው ዋሻ በጥሩ ሁኔታ ይሞቃል፣ በጎሽ ቆዳ የተደለደለው መደብ ተመችቶት አረፍ እንዳለ ጣፋጭ የሚዳቋ ወተት አቀረበለትና ጥሙን በወተቱ እያስታገሰ አይነት በአይነት ስጋ፣ አትክልትና ፍራፍሬዎች ደረደረለት። አቡሽ የቻለውን ያህል እራቱን ግጥም አርጎ በላና ለስላሳውን የድኩላ ቆዳ ደርቦ መደቡ ላይ ለሸሽ አለ።

ጠዋት ከንቅልፉ ሲነቃ አንበሳው ዋሻው አጠገብ ጋደም ብሎ ፀሃይ ይሞቃል። በሰላም ማደሩን ጠየቀውና አካባቢውን እያዟዟረ አስጎበኘው፣ ልጁም ባየው የደኑ ውስጥ ውበት በእጅጉ ተማረከ። ከዚያም አንበሳው ትንሹን ልጅ ጠራውና "በል እንግዲህ ይሄኔ ወላጆችህም ተጨንቀዋል በጊዜ ከጫካው አውጥቼ የቤትህን አቅጣጫ አሳይሃለሁ" አለው። ልጁ ግን ማልቀስ ጀመረ። "አልሄድም - አልሄድም ካንተ ጋር መኖር - እዚህ መሆን ነው ምፈልገው" እየተንፈራፈረ አለቀሰ። አንበሳውም "አልሄድም ካልክ ምን ይደረጋል? እዚሁ መኖር ትችላለህ - ብቻ ታማኝና ጥሩ ልጅ ሁን" አለውና አቡሽ ከአንበሳው ጋር መኖር ጀመረ።

የልጁ እናትና አባት ለብዙ ጊዜ ልጃቸውን በየጫካውና በየሃገሩ ሲፈልጉ ቆይተው ከአመታት በኋላ ጫካ ውስጥ ከአንበሳ ጋር የሚኖር ልጅ አለ የሚል ወሬ ሰሙና ለማረጋገጥ ወደ ጫካው ሄዱ። ልጃቸውን ዋሻው አጠገብ ሲጫወት አዩትና እየሮጡ ሄደው አቀፉት፣ ሳሙት "ልጃችን በህይወት ትኖራለህ የሚል ግምት አልነበረንም አንተ ግን ይኸው አድገህ፣ ወፍረህ፣ ተመችቶህ አገኘንህ - በል ወደ ቤታችን እንሂድ" አሉት። ልጁ ግን አንበሳውን እንደሚወደውና መኖር የሚፈልገውም እዚሁ መሆኑን ገልጾ በፈለጉ ጊዜ እየመጡ ሊጠይቁት እንደሚችሉ አስረድቶ ሸኛቸው።

ከዚያ በኋላ በየጊዜው እየሄዱ ይጠይቁታል፣ ወደ ቤታቸው ሲመለሱም አንበሳው እያደነ ከሚይዛቸው የዱር እንስሳት ሥጋ የጎሽ ሽንጥ፣ የድኩላ ታፋ፣ የአጋዘን እግር ይሰጣቸው ነበር። አንበሳውም የልጁ ወላጆች ሲመጡ በነፃነት እንዲጫወቱ ከዋሻው በስተኋላ በኩል ይተኛል። እንደተለመደው አንድ ቀን የልጁ እናትና አባት መጥተው ዋሻው ውስጥ ሲጫወቱ አባትየው "ልጄ እንደው እንዴት አድርገህ ከአንበሳው ጋር ተስማማህ? እስካሁን ምንም ችግር አልገጠመህም?" በማለት ጠየቀው። ልጁም "አባባ ሁሉም ነገር ጥሩ ነው፤ ነገር ግን የአንበሳው አፍ በጣም ይገማል ያስቸገረኝ ነገር ይኸው ነው" ብሎ መለሰለት። ከዋሻው ኋላ የተኛው አንበሳ ይህን ሲሰማ እጅግ በጣም አዘነ።

የልጁ ወላጆች ከሄዱ በኋላ ወደ ቤቱ የተመለሰው አንበሳ በእጁ ትልቅ ጦር ይዞ ነበር። ልጁን ጠራውና "ይህንን ጦር ጠበቅ አድርገህ ያዝና ተንደርድረህ ውጋኝ" ብሎ ጦሩን ሰጠው። ልጁ በፍጹም አላረገውም አንተኮ አባቴ ነህ እያለ እምቢ ቢልም፤ ማድረግ ስላለብህ አድርግ! የሚለው የአንበሳው ሃይለ ቃልና በቁጣ የደፈረሱ ዓይኖች ስላስፈሩት ተንደርድሮ ወጋው።

በቀጣዩ ቀን አንበሳው ከተኛበት መነሳትም ሆነ ከዋሻው መውጣትና ማደን አልቻለም። ውሎ ሲያድር እየተሻለው፣ ቁስሉ እየጠገገና እየደረቀ ከጥቂት ሳምንታት በኋላ ድኖ መንቀሳቀስ ጀመረ። ከወራት ቆይታ በኋላ በፀፀት ተቆራምዶ ዓይን ዓይኑን የሚያየውን ልጅ ጠራውና" አቡሽዬ - ና እስኪ - ቁስሌን ተመልከተው! እንዴት ነው? እየዳነ ነው?" በማለት ጠየቀው።

ልጁም ቀርቦ እየዳሰሰ ተመለከተውና "የሚገርም ነው ቁስሉ ድኖ፣ ጠባሳው እንኳ በፀጉር ተሸፍኖ፣ ካልዳበሱት አይታወቅምም - ሙሉ ለሙሉ ድኗል" አለው። አንበሳውም "በል ከፊት ለፊቴ ቁጭ በልና የምነግርህን በጥሞና ስማኝ" በማለት ቀጠለ።

"በጦር የወጋሽኝ መቼ እንደነበር ታስታውሳለህ?" ጠየቀው።

ልጁም - "እንዴታ ያንን መጥፎ እለት አልረሳውም፤ ቀኑን ወላጆቼ ሊጠይቁን መተው ነበር" መለሰለት።

አንበሳው - "አዎን ልክ ነህ፤ የዚያን እለት አንተና ወላጆችህ ዋሻው ውስጥ ስትጫወቱ እኔ ኋላ በተኛሁበት ድንገት ከእንቅልፌ ነቅቼ የሰማሁትን ማመን አልቻልኩም ነበር፣ ትዝ ይልሃል? አፌ በጣም እየሸተተህ እንደተቸገርክ ለአባትህ ነገርከው፣ ከፉኛ መንፈሴ ቆሰለ! ተጎዳሁ!። በጦር እንድትወጋኝ አደረኩ፣ ይኸው አሁን እንዳረጋገጥከው ቁስሌ ከወራት በኋላ ድኗል፤ ባንተ ንግግር የቆሰለው መንፈሴ ግን አልዳነም፤ እንዳመረቀዘ አለ። እንደ ጦሩ ቁስል ጊዜ አላደረቀውም - ከቶ ሊያድነውም አይችልም። ለዚህ ነው የናንተ ሰዎች "የአፍ ወለምታ በቅቤ አይታሽም" የሚል ተረትና ምሳሌ የሚጠቀሙት።

ምንጊዜም ከአፍህ በሚወጣ ቃል ሌሎችን አታስቀይም፣ አሳልፈህ ከማማት በቀጥታ ንገራቸው። ይህንን ጥልቅ እውነታ ይዘህ ከወገኖችህ ጋር ኑር፣ የህይወትህ መርህም አድርገው "በማለት ነገረውና ወደ ወላጆቹ መንደር ሸኘው። አቡሽ ከሚወደው ጫካ እያዘነና እየተከዘ ወጣ። ወደፊት በሚጠብቀው ኑሮ ውስጥ ከተመሳሳይ ስህተቶች የመራቅ ውጥኑን እያብሰለሰለ በዝግታ ሲጓዝ ቆይቶ ቤቱ ሲደርስ ጀምበር ጠልቃ ደንገዝገዝ ብሎ ነበር።

አዎን - የእግርን ወለምታ፣ የእጅና መገጣጠምያዎችን ውልቃት በቅቤ አሽተው፣ በእራፊ ጨርቅ አስረው ካቆዩት ይድናል። አንዴ ከአፍ ያመለጠ ክፉ ቃል፣ ስድብ፣ ሃሜት፣ ስብቀትና ወዘተ . . . ግን በምንም አሽተው የማያድኑት፣ እንዴትም አድርገው የማይመልሱት የዘላለም ወለምታ፣ ጊዜና ቆይታ የማይሽሩት ስብራት ነውና ከመናገራችሁ በፊት አርቃችሁ አስቡ። ምን ጊዜም ክፉ ቃል ከአፋችሁ እንዳይወጣ ተጠንቀቁ። ምላስ መከበርያም መዋረጃም ናት !።

ምንጭ ፦ አባታችን ግራዝማች ጴጥሮስ ዮሳ ገብርኤል ከ 40 ዓመት በፊት ከተረኩልን በርካታ ተረቶች አንዱ፤ እኔ እንደማስታውሰው ፃፍኩት።

ከልብ አመሰግናለሁ !



## ፍንጃሉ

ባልና ሚስቱ እጅ ለእጅ ተያይዘው በለንደን አውራ ጎዳና ዳርና ዳር በተኮለኮሉት ግዙፍና ዘመናዊ ሱቆች እየተዘዋወሩ የሚገዙትን እቃ ይመርጣሉ። ጊዜው ለጥንዶቹ የተለየ ነበር - የጋብቻቸው ሃያ አምስተኛ ዓመት ክብረ በአል። ወደ ለንደን የበረሩትም አስደናቂና ለየት ያለ የሸክላ ውጤት በተለይ እንደ የሻይ ስኒ (ፍንጃል) ወይም ማቅረብያ የመሳሰሉትን ለመግዛት ነበር። ፍለጋቸውን ቀጥለው በሁለተኛው ቀን አንድ ሰፊ የስጦታ እቃዎች መደብር ውስጥ እንደገቡ፣ ፊት ለፊት የተመለከቱት የሻይ ስኒ የሁለቱንም ቀልብ ሳበ። ወንድየው፤ "አቤት እንዴት ያምራል? እንደዚህ አይነት ውብ ጥበብ የፈሰሰበት ስኒ ይኖራል ብዬ አልገምትም" በማለት አድናቆቱን ሲገልጽ፣ በግርምት ታስተውል የነበረችው ሚስት፣ ወደ መደብሩ ሰራተኛ ዞራ፤ "እባክሽ፤ ይህንን የሻይ ስኒ ማየት እንፈልጋለን - ታቀብይን?" በማለት ጠየቀቻት።

የመደብሩ ሰራተኛ በጥንቃቄ ከመስታዎቱ መደርደርያ ውስጥ አውጥታ እንደሰጠቻት፤ በእጆቿ መዳፎች መሃል የተቀመጠው የሻይ ስኒ ተአምር ፈጠረ። አፍ አውጥቶ ይናገር ጀመር። በድንጋጤ የፈዘዙት ጥንዶችም ማዳመጣቸውን ቀጠሉ . . .

"ስለ እኔ አታውቁም! ያልተረዳችሁት ብዙ ነገር አለ - ስሙኝ!" አለና ቀጠለ "ሲጀመር የሻይ ስኒ አልነበርኩም ሆኜም አልኖርኩም። ወዳጆቼ! ያኔ ገና መሬት ምሰው የሚያወጡኝ ደቃቅ የሸክላ አፈር ነበርኩ። አሊቃየ ካለሁበት አምጥቶ ያሸኝና ያቦካኝ ጀመር፣ እየደጋገመ ሲጠፈጥፈኝና ሲጠቀልለኝ ራሴን መቆጣጠር አቃተኝና ኡኡታዬን ለቀቅሁት፤ እንዲተወኝ ተማፀንኩት። እሱ ግን ፈገግ ብሎ . . . "ጊዜው ገና ነው" አለኝ።

ቀጠለና በሚሽከረከር ነገር ላይ አስቀመጠኝ፣ ድንገት መሽከርከር ጀመርኩ፣ ፍጥነቱ እየጨመረ ስሽከረከር - ስሽከረከር ጦዝኩኝ፣ አዞረኝ . . . አቁመው - አቁምልኝ ሊያስመልሰኝ ነው! እያልኩ ብጮህ - ባለቅስ፤ አሊቃየ ራሱን በማነቃነቅ . . . ጊዜው እንዳልደረሰ አሳወቀኝ።

መች ሊያበቃ አንስቶ የጋለ ምድጃ ውስጥ ከተተኝ፣ እንደዚህ ያለ ሙቀትና መለብለብ አጋጥሞኝ አያውቅም። ምነው ምን በድዬው ነው ሊያቃጥለኝ የተነሳው? የሚል ሃሳብ መጣብኝ። መላ ሰውነቴ ጋመ፣ ግለቱ ሲያንገበግበኝ፤ እሪታየን አቀለጥኩት፣ ተንጠራርቼ መዝጊያውን አንኳኳሁ። የሚለው ባይሰማኝም ላቦት ባወረዛው መስታወት ውስጥ አጮልቄ አየሁት፣ ከከንፈሩ እንቅስቃሴ እንደተረዳሁት . . . "ጊዜው ገና ነው" ነበር።

በመጨረሻ በሩን ከፍቶ አወጣኝና መደርደርያው ላይ አስቀመጠኝ። እሰይ፤ቀስ እያለ አካሌ ሲቀዘቅዝ የተሻለ ምቾት ተሰማኝ። አዟዙሮ ጠራረገኝና ብሩሹን የተለያዩ የቀለም ጣሳዎች ውስጥ እያጠቀሰ ይቀባኝና ያኳኩለኝ ጀመ። የቀለሙና የመበጥበጫው ሽታ ግን አይጣል ሆነ። አፈነኝ፣ ማቅለሽለሽና መጓጓጡ ሲብስብኝ አስተዛዝኜ እንዲተወኝ ለመንኩት። የአሊቃዬ መልስ ግን በለሆሳስ "ጊዜው ገና ነው" የሚል ሆነ።

ድንገት አፈፍ አድርጎ ምድጃው ውስጥ መለሰኝ . . . አቤት እቶን ይህኛው ከቅድሙ እጥፍ ጊዜ ይበልጣል። ነደድኩ፣ ትንፋሽ አጣሁ፣ ወላፈኑ አመቀኝ . . . በለቅሶና በጩኸት የታጀበ ልመናየን አዥጎደጎድኩ፤ እሱ ምን ግዱ አሁንም የተለመደ መልሱን ሲናገር ከከንፈሩ አነበብኩ . . . ያው "ጊዜው ገና ነው" እንዳለኝ ተረዳሁ።"

ምንም አማራጭ እንደሌለኝ አወቅሁ፣ በተስፋ መቁረጥ ተረትቼ . . . እቺን ቅጽበት የሚሻገር ቅንጣት አቅም አልተረፈኝም፣ በቃኝ - አበቃልኝ ብየ ስደመድም ድንገት በሩ ተከፈተ። በዝግታ አንስቶ ወደ መደርደርያው መለሰኝና ክፍሉን ለቆ ወጣ። ደቂቃዎች እያለፉ፤ ቀዝቃዛው አየር እየነፈሰብኝ ባለሁበት ለአንድ ሰአት ያህል እንደቆየሁ . . . አሊቃዬ አንድ ክብ የፊት መስታወት ይዞ መጣና እንድመለከትበት ሰጠኝ። ድንቅ - ድንቅ . . . እጹብ ድንቅ! እኔ ለመሆኔ ተጠራጠርኩ፤ ፍጹም ተቀይሬአለሁ፣ የማይታመን ውበት ተጎናጽፌአለሁ። እኔ . . . እኔ መስታዎቱ ላይ ያፈጠጥኩት እኔ . . . እጅግ በጣም አምራለሁ።

ከፊት ለፊቴ ቆሞ የሚያስተውለኝ አሊቃዬ መናገር ጀመረ . . .የድምጹ ቃና፣ የቃላቶቹ አደራደርና ጥልቅ መልእክት አንዴ ከተደመጠ እስከ መቃብር የማይዘነጋ የመንፈስ ስንቅ ነበር። አንዲትም ቃል እንዳልረሳሁ እርግጠኛ ነኝ። እንዲህ አለ . . ." "ዘወትር እንድታስታውሰው እሻለሁ!" በማለት ቀጠለ "መታሸት፣ መጠፍጠፍና መጠቅለል ምን ያህል እንደሚያም አውቃለሁ። ይሁንና እንደዛው ትቼህ ቢሆን ኖሮ በነበርክበት ደርቀህ ትቀራለህ፣ የደረቀን ማስተካከል ደግሞ የማይሞከር ነው። በከፍተኛ ፍጥነት ስትሽከርከርም እንደሚያዞርህ፣ ለማስመለስ እንደሚተናነቅህና ሁለመናህ እንደሚታወክ ጠንቅቄ የምረዳው ሃቅ ነው። እናም በዚያ ሁኔታ ባቆም ኖሮ የአሁኑ ቅርጽህ የለም፣ ተጨማደህና ተፈረካክሰህ ትቀር ነበር።

ከእሳትም የሚዘጋ ምድጃ እንዴት እንደሚያቃጥል ጠፍቶኝ መሰለህ? ሙቀቱና መለብለቡ የሚያስከትለውን ስቃይ በሚገባ አውቃለሁ። ነገር ግን እዚያ ምድጃ ውስጥ ባልከትህ ኖሮ - ትሰነጠቃለህ፣ የተሰነጠቀና የተተረተረ ደግሞ ምን ይጠቅማል?። በክፉ ሽታ መታጠንም እጅግ ከባድ ነው። እርግጥ ብሩሼን እያጠቀስኩ በቀለማት ሳሳምርህና ስቀባህ በባእድ ጠረን ታፍነህ ተሰቃይተሃል፣ ያ እንደሚሆን አላጣሁትም። እንዴት አድርጌ ልተውህ? ብተውህ ይህ የምታየው ልዩ ውበት የማይታሰብ ሲሆን፣ ባንፃሩ በቀላሉ የምትረታ፣ ህይወትህን ሙሉ ምንም የማታምር፣ ቀለም አልባና መልከ ጥፉ ሆነህ ትኖር ነበር።

ለሁለተኛ ጊዜ መልሼ እንደዛ የሚያንገበግብ ምድጃ ውስጥ እንድትቆይ ያደረኩት ለምን እንደሆነ ታውቃለህ?። ድርጊቴ የግድ መሆን ስላለበት ላንተው ነው። እንደዚያ ባላደርግማ . . .  መከራና ችግርን ተቋቁሞ ለረጅም ጊዜ የመጽናት ጥንካሬን ባልተቀዳጀህ ነበር። አዳጋች ፈተናዎችን ማለፍና ብቃትን ማረጋገጥም ይኸው ነው። አሁን አንተ በሚገባ ተሰርቶ የተጠናቀቀ ውጤት ነህ። እውነቱን ለመናገር ልክ - ቀደም ብየ በአእምሮዬ እንደሳልኩትና መጀመርያ እንደወጠንኩት ሆነህ ተቀምጠሃል" አለኝና በለስላሳ ወረቀት ሸፍኖ አዲስ ፓኬት ውስጥ ከተተኝ፣ ይኸው ነው እንግዲህ እናንተም እንደምታዩት እዚህ አለሁ" በማለት የሻይ ስኒው ተአምረኛ ንግግሩን አበቃ።

ታሪኩም አበቃ። ከዚህ በላይ ስለጥንዶቹም ሆነ ስለግብይቱ የተባለ ነገር ስላላገኘሁ የምለው የለኝም። የታሪኩ አስኳል መልእክት ግን በሚገባ ስለመተላለፉ እርግጠኛ ነኝ። የትንቢተ ኤርምያስን ምዕራፍ 18 ከቁጥር 1 – 6 መልእክትን ዋቢ በማድረግ እንቀጥል . . . ምንም ነገር የማይሳነው ፈጣሪ አምላክ በእኛ ላይ የሚያደርገውን ሁሉ ያውቃል፣ ቅንጣት የተሰወረ ነገር የለም። (አለቃው) ፈጣርያችን- <u>እሱ ሸክላ ሰሪው ነው።</u>  <u>እኛ ደግሞ ሸክላዎቹ ነን</u>። ቀርጾ፣ አስተካክሎና አሳምሮ ሰርቶናል። እናም እንከን የለሽ ፈቃዱ ይፈፀም ዘንድ ፍጹም ተመሳሳይ የሆነው ውጤቱ በማያቋርጥ ሂደት መመረቱን ቀጥሏል። ማናችንም ይህንን ሂደት ማለፍም ሆነ መዝለል አይቻለንም።

ይህ ታሪክ በቀላሉ ልናስታውሰው የሚገባ እጅግ ጠቃሚ መልክት አስተላልፏል። ኑሮ ከበድ ሲል፣ ፈተናዎች ሲበዙና መሸከም ከምንችለው በላይ . . .  ሲሆንብን ልናስበው የሚገባን አብይ ቁም ነገር። ይኸውም ሸክላ ሰሪው ሸክላዎቹን በፈተናዎች ውስጥ ማሳለፉ ምክንያት እንደነበረው መረዳትና አዲስ ሳይሆን የሚጠበቅና እያንዳንዳችን የታደልነው መሆኑን ማወቅ ነው። ወዳጆቼ :- ከአንድ ቦታ ተቆፍሮ ለመመረት የተዘጋጀው ጥሪኝ የሸክላ አፈር የሁላችንንም አፈጣጠርና መነሻ ፍጹም ተመሳሳይነት ሲያመላክት፣ ሸክላ ሰሪው በአንድ መዘውር ላይ አስቀምጦ በእኩል ፍጥነት ያሽከረከረው ቡኬት ደግሞ በመሰረታዊ ቅርጽና ውስጣዊ ችሎታ የተሰጠንን የጋራ ባህሪይ  ይገልፃል።

የተለያየው መልካችን፣ ጥቁረትና ንጣታችን የህብረ ቀለምን ውሁድ ፍካትና አስደናቂ ውበት በብሩሹ አሳምሮ ቀባን። በክፉ ሽታ ከመታፈን አንስቶ በእቶን የእሳት ረመጥ የተፈተሸው ማንነታችን ደግሞ ሁላችንም እልህ አስጨራሽ ፈተናዎችን ተሻግረን፣ መከራን የማሸነፍ ብቃትና ጥንካሬን ያለ አንዳች መድሎ እኩል እንደታደልን ቁልጭ አድርጎ ያሳያል። የምድር ላይ ውሏችን ለየቅል ሆኖ በስኬትና ውጤታማነት መለክያ መበላለጣችን ከወዲህ እንጂ አብሮን ያልመጣ ስለመሆኑ ከዚህ ወዲያ ምን ማስረጃ ይገኛል?። በየትኞቹም የማወዳደርያ መስፈርት ነጥቦች፣ ካለመሞከር፣ ካለመጣር፣ ተስፋ ከመቁረጥና . . . ወዘተ ከመሳሰሉት አሉታዊ እሳቤዎች በስተቀር አንድ አምሳል፣ አንድ አካል፣ ፍጹም እኩል ተፈጥሮና ብቃት ተጎናጽፈን ስለመወለዳችን የሻይ ስኒው ታሪክ  ከበቂ በላይ ነቃሽ ነው! እላለሁ።

አመሰግናለሁ !

ምንጭ :  (http://www.creativebiblestudy.com)
This teacup story illustrates what Jeremiah wrote by the inspiration of God (Jeremiah 18: 1 - 6)
(ትንቢተ ኤርምያስ ምዕራፍ 18 ከቁጥር 1 – 6) እንደ መነሻ ሃሳብ ተወስዶ የተፃፈ
ደራሲው : ያልታወቀ        *       ጥር  -  2007 ዓ. ም.  *   አዲስ አበባ

## <u>"የነፍስ ዋጋ"</u>

ቀደም ባለው ጊዜ አራት ሚስቶች ያሉት አንድ ባለፀጋ ንጉስ ነበር።

አራተኛ ሚስቱን ይወዳታል። ወዘናና አቋሟ እንዲጠበቅ ይንከባከባታል። በወርቅና አልማዝ አስውባታል፣ እጅግ ውድ በተባሉ ጌጦች የተንቆጠቆጠ ካባ ያለብሳታል። እንኪ ብሎ ቆጥሮ ባይሰጣትም ከሚያስፈልጋት በላይ ምቾትና ቅንጦትን ይለግሳታል።

ሦስተኛ ሚስቱንም ይወዳታል፣ ለጉብኝት በወጣበት ሁሉ ያስከትላታል፣ ከጎረቤት መንግስታት መሪዎችና ልኡካን ጋር በሚደረጉ መንግስታዊ ጉዳዮች ላይ ተገኝታ ጎልታ ስትታይ ደስ ይለዋል ። ሆኖም አንድ ቀን ጥላው እንደምትሄድ ስሜቱ እየነገረው ፍርሃት ፍርሃት ይለዋል።

ሁለተኛ ሚስቱንም ቢሆን ይወዳታል፣ በጣሙን ይመካባታል፣ ሁሌም ለሱ ትሁት፣ ቅን አሳቢና አስታራቂ ስለሆነች ይተማመንባታል። ንጉሱ – አንገብጋቢ ችግሮች ሲገጥሙትና ከውስብስብ መሰናክሎች ጋር ሲጋፈጥ ምክርና መፍትሄ ፍለጋ የሚሄደው ወደ እርሷ ነው።

አንደኛዋ የንጉሱ ሚስት እንከን የማይወጣላት ታማኝና ትክክለኛ አጋር ናት። በመንግስቱ የመዋቅር ግንባታ ሂደት ውስጥ ከፍተኛውን ድርሻ ያበረከተችና ለካበተው ሃብቱ ብዙ የደከመች ሃቀኛ ሴት ነች። ይሁን እንጂ እሱ አይወዳትም፤ እሷ ግን ለእርሱ ያላት ጥልቅ ፍቅር የማይቀየየር ነው። ንጉሱ ምንግዜም በከባድ ማስጠንቀቅያና ጥርጣሬ ያያታል።

አንድ ቀን ንጉሱ በጠና ታመመ፣ ህይወቱ አደጋ ውስጥ እንደሆነችና የጥቂት ቀናት ቆይታ ብቻ እንደቀረው ተረዳ። ስለተቀማጠለ ኑሮው፣ ስለ ተትረፈረፈ ሃብቱና ገደብ የለሽ ስልጣኑ አጥብቆ አሰበና “አሁን ከአንድም አራት ሚስቶች አሉኝ፣ በቅርቡ ስሞትና ወደ መቃብር ስገባ ግን ማንም አጠገቤ አይኖርም ብቻዬን . . . ብቻዬን ነኝ” በማለት ተሳቀቀ። በዚህ ሁኔታ እየተብሰለሰለ አራተኛ ሚስቱን እንዲጠሩለት ትእዛዝ አስተላለፈ። ተጠርታ እንደቀረበች . . .

“እንደምወድሽ ታውቂያለሽ፣ በከፍተኛ ጥንቃቄና ምቾት እንክብካቤ እየተደረገልሽ፣ በውድ ጌጦችና ልብሶች ተውበሽ፣ አምረሽ ደምቀሽና ተንቀባረሽ እንድትኖሪ አድርጌአለሁ። አሁን ግን በሞት ልለይሽ ነው፣ ትከተይኛለሽ? አብረሽኝ ትሆኚያለሽ?” ሲል ጠየቃት። አራተኛዋ ሚስት “በምንም መንገድ አይሆንም!” በማለት ሌላ ምንም ሳትናገር ጥላው ወጣች። መልሷ ልቡን በሥለት የተወጋ ያህል አሳመመው። ቅር እንዳለው ሦስተኛዋን ሚስት አስጠራና ቀጠለ . . .

“ሕይወቴን ሙሉ ስወድሽ ኖሬአለሁ፣ በወጣሁበትና በገባሁበት ሁሉ አስከትየሽ እንድትታይና እንድትደነቂ ሳደርግ ቆይቻለሁ። ይኸው ሞቴ ቀረበ በማለፍ ላይ ነኝ፣ አብረሽኝ ትመጪያለሽ? ታጅቢኛለሽ?” በማለት ጠየቃት። ሦስተኛዋ ሚስት ”አይሆንም!። አንተ ስትሞት ሌላ ማግባት እንደምችልና ሕይወት የበለጠ ጣፍጣኝ እንደምኖር እንዴት አይታወቅህም?” አለችው። በረዶ እንደተደፋበት ሰው መላ ገላው በቅዝቃዜ ተንዘፈዘፈ። ከዚያም ሁለተኛ ሚስቱ እንድትመጣ አስደርጎ ጠየቃት . . .

“እድሜ ዘመኔን እርዳታና ምክርሽን ፍለጋ ወደ አንቺ በዞርኩ ቁጥር አንቺም በአስፈላጊው ስፍራና ጊዜ ሁሉ ተገኝተሽልኛል። ከጎኔ ሆነሽ በሚገባ ረድተሽኛል። ከዚህ ዓለም በሞት ስለይስ ከኔ ጋር ትሆኚያለሽ? ትመጪያለሽ?” አላት። ሁለተኛዋ ሚስት “አዝናለሁ! – በጣም አዝናለሁ! ይህኛውን ጊዜ አብሬህ ልሆንና ልረዳህ አልችልምና አትጠይቀኝ” አለችውና አያይዛ ”ላደርግልህ የምችለው የመጨረሻ ነገር ቢኖር ወደ መቃብር ስትሄድ አሸኛኘት ማድረግ ነው” በማለት በዝግታ መለሰችለት። ንጉሱ የሁለተኛ ሚስቱ ንግግር መሃል አናቱን በመዶሻ የተመታ ያህል አሳመመው፣ ዞረበት ብልጭልጭ ቀለማት አይኖቹን ሲያጥበረብሩት ሁሉም ነገሩ እንደወደመ ተሰማው። በተቀመጠበት አንገቱን በትካዜ ደፍቶ በሃሳብ . . . ነጎደ።

በዚህ መሃል ድምጽ ሰማ “እኔ አብሬህ እሆናለሁ! የትም ይሁን የት ግድ የለኝም፣ በሄድክበት ሁሉ እከተልሃለሁ . . . ” ቀና ብሎ ተመለከተ – አንደኛዋ ሚስቱ ነች። ስጋ የተባለ ነገር አይታይባትም፣ በምግብ እጦት ከፉኛ መጎዳቷ ያስታውቃል፣ሰውነቷ እጅግ በመከሳቱ ቆዳ የለበሰ አጽሟ ያስፈራል። ከመቃብር ሸሽታ ያመለጠች ጣእረ ሞት ትመስላለች።

ንጉሱ በሃዘንና በፀፀት ተኮማትሮ እንዲህ አለ . . . “አማራጩ በነበረኝና ብዙ ማድረግ በምችልበት ሰአት፤ የበለጠ ክብካቤና የተሻለ ትኩረት መስጠት የነበረብኝ ላንቺ ነበር። ነገር ግን . . . ሳላደርገው ኖርኩ፣ አሁንማ ሁሉም አለፈ፣ ረፍዶብኛል፤ በቃ . . . በቃ” በማለት የመጣውን ለመቀበል ወስኖ ዝም አለ።

ስለ እውነት ሁላችንም በዚህች ዓለም የህይወት ቆይታችን ውስጥ አራት ሚስቶች አሉን፣ (እንስት አንባቢዎቼ አራት ባሎች በሚለው እየተካችሁ አንብቡት)። አማላጅ ሽማግሌ ሳንልክ፣ ሳናጭ፣ ቀለበት ሳናጠልቅ፣ በሰማንያም ሆነ በሌላ ሕገ ጋብቻ ሳንፈራረምና ሳንሰርግ ያገባናቸው ከአንድም አራት ሚስቶች (ባሎች)። እንዴት ነው ነገሩ? . . . አራት! አይዟችሁ፤ ግር አይበላችሁ፤ ይኸው ልነግራችሁ ነው።

የኛ አራተኛ ሚስት – አካል ገላችን ነው። ምንም ያህል ጊዜአችንን ሰጥተን፣ የትኛውንም ያህል ገንዘብና ሃይላችንን አባክነን ብንኩል – ብናሳምረው፣ ብናስጌጥ – ውብ ብናደርገው ስንሞት ጥሎን ይሄዳል። አለምን ስንሰናበት እሱም ወደ ቀድሞ መነሻው ይወርዳል።

የኛ ሦስተኛ ሚስት – ስልጣናችን፣ ሃብትና ገንዘባችን ነው። በምድራዊ ኑሯችን ያፈራነው፣ ቀምተንም ይሁን ደክመን ያካበትነው፤ ንብረትና ንዋይ የሌላ ይሆናል። ተፈልገንም ይሁን ፈልገን፣ በሃቅ ተመርጠንም ሆነ በሃሰት አጭበርብረን የተቆናጠጥነው የስልጣን ወንበር ሌላ ይቀመጥበታል። ጊዜ ፈቅዶ እጃችን የገባ፣ እውነት የፈረድንበት አልያም ምስኪኖችን የቀጠቀጥንበት የፍትህ መዶሻ፤ ሳንወድ በግድ ለሌላ ይተላለፋል።

የኛ ሁለተኛ ሚስት – ቤተሰብ፣ ዘመድና ጓደኞቻችን ናቸው። ለዘመናት አብረውን ቆመዋል፣ ድጋፍ ግሳፄና ምክራቸውን እየለገሱ አብረውን ኖረዋል። የመጨረሻ ቆይታቸው ከቀብራችን ቀጥሎ፣ ውሏችንን የማይመስለው የሕይወት ታሪካችን በጣፈጡ ቃላት ተከሽኖ በንባብ ከተሰማ በኋላ እዛው ላይ ይጠናቀቃል፣ በማሳረግያው ሸኝት ያበቃል።

የኛ የመጀመርያ ሚስት – ነፍሳችን ናት። ስጋችንን አስበልጠን፣ ብቃቷን ንቀንና ከእለታዊ ኑሯችን አግልለን፤ ከነ መኖሯም የረሳናት። ለዓለምና ዓለማዊ ውጥኗ ሰግደን፣ ራሳችንን አስገዝተንና ገብረን፣ ለሰማያዊው እስትንፋሳችን ማደርያ የሚበጅ አንዳችም በጎ ምግባር ሳንፈጽም፣ እድሜ ዘመናችንን በእንቶ ፈንቶ ፈጅተን ወደ ፍፃሜአችን ስናመራ አብራን የምትጓዘው (የመጀመሪያዋ ሚስት) - ነብሳችን ናት። እስከመጨረሻው የምትከተለን፣ ከፍርዱ መድረክ የምትደርሰውና ከዳኛው መንበር የምትቆመውም ነፍሳችን ብቻ ናት። እናም በዚህች ምድር ላይ እያለን ከፍተኛውንና ከሁሉ የላቀውን ክብር ለነፍሳችን እንስጥ። ሕይወታችን እውነት የተዘራበት፣ መልካም ቡቃያ የፋፋበትና ሰናይ ፍሬ የጎመራበት መስክ ይሆን ዘንድ፤ በበጎ ምግባር ኮትኩተን፣ በጽድቅ ተግባር አለምልመን እናጽናው። የምንፈራበትን ሳይሆን የምንኮራበትን ገድል አኑረን፣ በድን አካላችንን ከተጫነው አፈር ላይ የሚቆም የድንጋይ ሃውልት ሳይሆን ትውልድ የሚዘክረውን ትክክለኛና አንፀባራቂ የነፍስ ዋጋ አኑረን እንለፍ።

የነፍስን ዋጋ ለመተመን ብዙ ርቀት መሄድ አያስፈልግም፣ እዚሁ አጠገባችንና አብሮን ያለ ነው። ለበጎ ነገር መትጋት፣ ሌሎችን መርዳት፣ ጉዳታቸውን በመጋራትና ቀምበራቸውን በመሸከም ከጎናቸው መቆማችንን በሚያረጋግጥ ተግባር ማገዝ ነው። ለእውነት የተገዛ - በእውነት የሚያምን ሰው ለመሆን በመጣር ሂደት ውስጥ የሚካተቱ ሁላችንም ጠንቅቀን የምናውቃቸው . . . ነገር ግን ለመተግበር ሁሌም ዳገት የሚሆኑብንን ቅን ጉዳዮች ጨክኖ መፈፀም ነው!።

ወዳጆቼ፡- ያኔ ነው ርሃብ በአጥንቷ ያላስቀራትና አለም ያላጎሳቆላት፣ ጽኑ፣ ፈርጣማና ጠንካራ ነፍሳችን ቀና ብላ፤ በፍጹም የራስ መተማመን አብራን የምትራመደው። ያኔ ነው የትም ይሁን የት እስከመጨረሻው የምትከተለንና በጽድቅ መንደር አብራን የምትሆነው። ልብ በሉ! . . . መምጫው አይታወቅም፣ ቀጠሮም ሆነ ምልክት አይሰጥም። ልጣችን ሳይራስ – ጉድጓዳችን ሳይማስ - አስቀድመን፣ ጊዜ ሳንሰጥ - ፈጥነን፤ ዛሬ መጀመር ነው . . . ዛሬ . . . አሁኑኑ . . . አ ሁ ን።

ምንጭ ፡ ”የደስታ ዘመን ማስታዎሻ” የሮበርት ኤል. ዋይሌይ መጽሃፍ ”የነፍስ ዋና ጥቅም” ከሚለው ርእስ
Source ፡ “REMINISCENCES OF HAPPY TIME” book by: Robert L. Wiley
Title: “Importance of Soul”

ግንቦት - 2008 ዓ. ም. * አዲስ አበባ







## ጭልፊቷና ቅርንጫፉ

አንድ ንጉስ ሁለት እጅግ የሚያምሩ ጭልፊት አሞራዎች ራቅ ካለ የግዛቱ ክፍል በስጦታ ተበረከቱለት። ንጉሱ እንደነዚህ አይነት ግራጫ ክንፍ ያላቸው ጭልፊቶች ከዚህ ቀደም አይቶ አያውቅም ነበርና በስጦታው በመደሰት ዋናው የጭልፊቶች አሰልጣኝ ያሰለጥንና በጥንቃቄ ይከታተላቸው ዘንድ አስረከበው።

ከቀናት በኋላ ዋናው አሰልጣኝ ወደ ንጉሱ በመቅረብ አንዱ ጭልፊት በከፍተኛ ፍጥነትና ግርማ ሞገስ ቤተ መንግስቱን ዞሮ ወደ ላይ በመመንጠቅ ሰማዩን አስሶ ይመለሳል፣ አንደኛዋ ግን ከመጣች ጀምሮ ከተቀመጠችበት ቅርንጫፍ ላይ አልተነሳችም። በበኩሌ የአቅሜን ሁሉ ሞክሬ አልሆነልኝም በማለት ሁኔታውን አሳወቀው።

ንጉሱም በመላ ግዛቱ ውስጥ የሚገኙ ጠቢባን፣ ሃኪሞች፣ ፈላስፎችና ምትሃተኞች ሳይቀሩ እየቀረቡ ጭልፊቷ ካረፈችበት ቅርንጫፍ ላይ ተነስታ እንድትበር የተቻላቸውን ሁሉ እንዲያደርጉና እንድትበር ያደረገውን ሰው እንደሚሸልም አዋጅ አስነገረ። ይሁን እንጂ ማንም ጭልፊቷን እንድትበር ማድረግ አልቻለም። በመቀጠል ምክር ቤቱንና የበታች ሹሞቹን ሰብስቦ ሁሉም እንዲሞክሩ አዘዛቸው። በነጋታው በእልፍኙ መስኮት ሲመለከት ጭልፊቷ ከተቀመጠችበት ቅርንጫፍ ላይ አልተነሳችም።

ንጉሱ “ያልተሞከረ ምን አለ?” በማለት ሲያስብ ቆየና “ምናልባት ራቅ ካለው የገጠር ክፍል የተፈጥሮን ሁኔታ ይበልጥ የሚገነዘብ አንድ ሰው ይህንን ችግር ሊፈታው ይችል ይሆናል” የሚል ሃሳብ ብልጭ አለለት። ወዲያውም ባለሟሎቹን ጠርቶ በአስቸኳይ አንድ ገበሬ ከገጠር እንዲያመጡና እንዲሞክር እንዲያደርጉ ትእዛዝ አስተላለፈ።

በቀጣዩ ጠዋት ከእንቅልፉ እንደነቃ ወደ ደጅ የወጣው ንጉስ በሚያየው ነገር ከመጠን በላይ ተደነቀ። ጭልፊቷ በቤተ መንግስቱ የአትክልት ሥፍራ ላይ ከፍ ብላ የጠዋቱን ቀዝቃዛ አየር በክንፎቿ እየቀዘፈች ትበራለች። “የዚህን አስደናቂ ተአምር ፈፃሚ ምርጥ ሰው አሁኑኑ አቅርቡልኝ” ሲል ባለሟሎቹን ጠየቃቸው። ባለሟሎቹም ፈንጠር ብሎ ወደቆመው ገበሬ አመለከቱት።

“እንዴት ነው? ጭልፊቷ እንድትበር ያስቻልከው” በማለት ጠየቀው።

ገበሬው ወደ ፊት ቀርቦ እጅ በመንሳት . . . “ንጉስ ሆይ! እጅግ ቀላል ነው። እኔ ጭልፊቷ የተቀመጠችበትን ቅርንጫፍ በያዝኩት ፋስ ከመቁረጥ ሌላ የፈፀምኩት ምንም ነገር የለም” በማለት አስረዳ። ይባላል።

ሁላችንም ሰው እንደመሆናችን መብረር እንችላለን። በአስተሳሰባችን መጥቀን መውጣትና በአእምሯችን ውጤት ተጠቅመን በክህሎት እስከ ዳር መቅዘፍ አይሳነንም። በውስጣችን ያዳፈንነውን እምቅ፣ አስገራሚና ተአምረኛ ሃይል አውቀን በመጠቀም፤ ወይም ሳንረዳው በመቅረት ጥቂቶች ይበራሉ ብዙዎቻችን ግን ያረፍንበትን ቅርንጫፍ የሙጥኝ እንዳልን በተቀመጥንበት ቀርተናል። ማለቂያ የሌላቸው አማራጮች፣ ቁጥር ስፍር የሌላቸው መፍትሄዎች እያሉ ለአብዛኛዎቻችን አይታዩንም፤ ዙሪያችንን ከከበበን ድባብና ካለንበት ሁኔታ ጋር እጅግ በመላመዳችን፤ አንዳንዴ ትሻቸው ተደብቀውብናል። የዕለት ተለት የህይወት ዘመናችንን በሚያነቃቃ አዲስ ግኝት፣ ተስፋን በተሞላ ጥረትና ተጨባጭ እርካታ ከመምራት ይልቅ፤ ተራ በሆኑ ነገሮች ላይ ስለምናተኩር ከስራችን ያለችውን ትንሽ ግን ግዙፍ ውጤት የምታቀዳጅ መፍትሄ ሳናገኝ፤ እስካሁን ባለንበት እንደ ነበርን ተቀምጠናል።

አርቀን እናስብ፣ ስብዕናችንን ለቁም ነገር እናትጋ፤ የተጋረጡብንን የስጋትና የስንፍና ቅርንጫፎች ቆራርጠን በነፃነት - እንብረር . . . እንብረር።

እስቲ ይህችን ቁም ነገር የሚያጠናክሯት ጥቂት ስንኞች እንደርድርላት . . .

**ፋስ የጨበጠ ሰው**

አዳኝም የለ - ገዳይም የለ - አለች አሉ የጨነቃት ወፊት
የሚያድናትም - የሚያድናትም - ጭራሽ በሌለበት
አናቷን ቀብራ ከንፎቿ ስር - ሞቷን ሰርቃ ላለማየት
ሙጥኝ ብላ ተቀምጣ - ቅርንጫፉን ተማምናበት

እንዳትበር ምኗን አምና - የገዛ ክንፏን ጠርጥራ
እንዳትሄድ ተቀይዳ - እግር ካንገት ተወጥራ
ወዲያ ወዲህ እንዳትፈትሽ - ዞርያ ገቡን እንዳትቃኝ
ብልሃት ስልቱን እንዳታቅድ - መፍትሄውን እንዳታገኝ

ማምለጫ ዘዴው ቢልቃት - የቅርቡን ማግኘት ቢገዳት
መንገድ ክፍተቱ ቢጠባት - አርቆ ማየት ቢርቃት
ፍርሃት ተብትቦ ቢይዛት - የጨለማ ካብ ቢደፋባት
ቁጭ እንዳለችው ቁጭ አለች - የምታደርገው ቢጠፋት

እየሰሙ ላለማድመጥ - እያወቁ ላለማድነቅ
የገሃዱን ለማዳፈን - የግላጩን ለመደበቅ
ከዚህ ወዲያ ምን መላ አላት  - መሸሸግያ ውሉ ሲርቅ
አማራጩም ይኸው ብቻ - በራስ ጥላ ሥር መደበቅ

አንዳንዴ ሳስበው - እኛና ጭልፊቷ - አንድ ነገር አለን
በሕይወት ኡደት ውስጥ - የሚየቀራርበን - የሚያመሳስለን
መነሳት አቅቷት - መብረሩንም ፈርታ - እንደጠረጠረች
እሷ ቅርንጫፉን - የሙጥኝ እንዳለች - ባለችበት - ቀረች

እኛም ምክራችን ላይ - እቅድ እየከመርን
ቀደን ስንሰፋ - በትነን ስንለቅም - እንዲያው ከዳር ቆመን
ወይ ደፍረን አንገፋ - ወይ ቆርጠን አልተውን
ኩርኩም ስንፈራ - እንቅፋት ሲያጎነን
ሰፌድ ስፍ ስንጓዝ - ቅንጣት ስንተነትን
ጥረታችን ከትሞ - መስኩ ላይ ተኝተን
ባለንበት አለን - አንነቃነቅም - እዛው ተጎልተን

ወፌስ ቅርንጫፉ ሲቆረጥ ተነሳች - በረረች . . . ከነፈች
ዛሬስ ቀናትና ፈለጓን አፀናች - ሄደች - አመለጠች . . .

የምድሩ ጎድጉዶ - የሰማዩ ርቆ - አልታይ እያለን
ጉልበታችን ዝሎ - ጽናታችን ባክኖ - ተስፋ እየራቀብን
ጨለማውን ገፎ - ድባቡን ጠራርጎ - መንገድ የሚያሳየን
ጎንታይ አመላካች - ከእንቅልፍ የሚያነቃ - ቀስቃሽ የጠፋብን

ቅርንጫፉን ጎምዶ - መንጥቆ የሚያስነሳ - ፋስ የጨበጠ ሰው
ያጣነው እኛ ነን - ማዘንስ ለኛ ነው - ምንም ለማንበጀው።

ምንጭ - Social Media - in Awakening, Moral Stories Collection
"The Falcon & The Branch"
ጿግሜ - 2007 ዓ.ም. ጂማ

## "ይቻላል ! . . ."

"የማይቻል ነገር የለም!"

ይህ እውነተኛ ታሪክ በግዙፉ የአለማችን ኩባንያ ጄኔራል ሞተርስ እና በአንድ ደንበኛው መሃከል የተፈፀመ አስገራሚ ታሪክ ነው።

በጄኔራል ሞተርስ የፖንቲያክ ንዑስ የስራ ክፍል ኃላፊ ከደንበኛው አንድ የቅሬታ ደብዳቤ ደረሰው።

"ይህ የቅሬታ ደብዳቤ ለሁለተኛ ጊዜ የላኩላችሁ ቢሆንም እስከ አሁን መልስ ባለማግኘቴ እናንተን አላማረርኩም። ምክንያቱም፤ የደብዳቤው መንፈስ ግር የሚልና ያልተለመደ በመሆኑ ሲሆን እውነታው ግን ለረጅም ጊዜ በቆየው ማታ ማታ አይስ-ክሬም የሙብላት የቤተሰባችን ልምድ በየምሽቱ እራታችንን ከተመገብን በኋላ አይነቱ በድምጽ ብልጫ ይወሰንና የእለቱን አይስ-ክሬም ለመግዛት ወደ ጣፋጭ መሸጫው ቦታ መኪናዬን እያሽከረከርኩ እሄዳለሁ።

ይሁን እንጂ እንደሚታወቀው በቅርብ ጊዜ ከኩባንያችሁ ከገዛኋት ፖንትያክ መኪና በኋላ በጉዞዬ ችግር እየገጠመኝ ይገኛል። ይታያችሁ - በየጊዜው ቫኒላ አይስ-ክሬም ከገዛሁ በኋላ ወደ ቤት ለመመለስ የመኪናዬ ሞተር አይነሳም፤ ሌላ የትኛውንም ዓይነት አይስ-ክሬም ከገዛሁ ግን ሞተሩ በጥሩ ሁኔታ ይነሳል፣ እኔ ይህ ጉዳይ የምር አሳስቦኛል!ጥያቄው የጅል ወይም ምንም መላ ቢስ ይምሰል ግድ የለኝም። ዋናው ነገር መኪናዬ ቫኒላ አይስ-ክሬም ስገዛ ሞተሩ አይነሳም፤ ሌሎቹን አይነቶች ስገዛ ግን በቀላሉ ይነሳል የሚለው ነው"።

- አመሰግናለሁ"
የኩባንያችሁ ደንበኛ

. . . ይላል። ምንም እንኳ የኩባንያው ፕሬዝዳንት ደብዳቤውን በጥርጣሬ መንፈስ ቢረዳውም፤ ለማንኛውም በሚል ሁኔታውን እንዲያጣራ አንድ ኢንጂነር ወደ ሥፍራው ላከ። የባለጉዳዩ ጎረቤት ለሆነው መልካምና የተማረ ሰው ምስጋና ይግባውና አንድ ምሽት ከእራት በኋላ ከ ኢንጂነሩ ጋር ይገናኙ ዘንድ ሁኔታዎችን በማመቻቸት ሁለቱም በተስፋ ወደ ጣፋጭ መሸጫው ሱቅ አቀኑ። እለቱ የቫኒላ አይስ-ክሬም ነበርና ገዝተው ወደ ቤት ለመመለስ መኪናው ውስጥ ገቡ፣ ነገር ግን ሞተሩ - አልነሳም አለ።

በቀጣዮቹ ሶስት ተከታታይ ምሽቶች ተመላልሶ ሞከረ፤ በመጀመሪያው ቀን ቼኮሌት አይስ-ክሬም ገዙ የመኪናው ሞተር ተነሳ፣ በሁለተኛው ቀን እንጆሪ ነበር የመኪናው ሞተር ተነሳ፣ በሶስተኛው ቀን ቫኒላ አዘዙ የመኪናው ሞተር አልተነሳም። ከዚህ በኋላ ኢንጂነሩ የዚህ ሰው መኪና ለ ቫኒላ አይስ-ክሬም እንደ አለርጂ የመታየቱን መላምት አስወግዶ በነባራዊው ሁኔታና ተያያዥ ጉዳዮች ላይ በማተኮር፣ የፈጀውን ያህል ጊዜ ወስዶ የችግሩን መንስኤ ከስሩ ለመረዳት ያስፈልጋሉ ያላቸውን ዘመናዊ የምርመራ ዘዴዎች ሊጠቀም ወሰነ። በዚሁ መሰረት እያንዳንዱን እንቅስቃሴና ድርጊት በመመዝገብ የተጣራ መረጃ ማዘጋጀትን ቅድሚያ ሰጥቶ ቀኑን፣ ሰአቱን፣ የአየሩን ሁኔታ፣ መኪናው የሚጠቀምበትን የነዳጅ አይነትና የተጓዘበትን መስመር፣ ለመሄድ ለመመለስና ለግዢ የወሰደበትን ጊዜ . . . ወዘተ የመሳሰሉትን መረጃዎች ባጠናቀረ አጭር ጊዜ ውስጥ ሰውየው ቫኒላ አይስ ክሬም ለመግዛት የሚወስድበት ጊዜ ከሌሎቹ ጣዕሞች ያነሰ መሆኑን አንድ ፍንጭ አገኘ።

ለምን ?፦ ምክንያቱን ሲያጣራ የጣፋጮቹ ማከማቻ የተለያየ ቦታ መሆኑ ነበር። ይኸውም ቫኒላ በአብዛኛው ደንበኛ የሚፈለግ በመሆኑ በፍጥነት ለማንሳት የተቀመጠው ፊት ለፊት ከሚገኘው መደርደሪያ ላይ ሲሆን የሌሎቹ ግን በጀርባ በኩል ከሚገኘው የተለየ ማከማቻ በመሆኑ፤ ከቫኒላ ጋር ሲነፃፀር ሌሎቹን ጣእሞች ለመግዛት የሚወስደው ጊዜ የረዘመ ይሆናል። አሁን በኢንጂነሩ አእምሮ ያልተመለሰው ጥያቄ "ቫኒላ አይስ-ክሬም ሲገዛ የመኪናው ሞተር ለምን አይነሳም?" ሳይሆን "አጭር ጊዜ ሲሆን መኪናው ለምን አይነሳም?" በሚለው ተተክቷል። ይህም ምርመራውን ከመላምት ወደ ተጨባጭ ሂደት የሚመራ በመሆኑ እሰየው !!! - ዩሪካ !!! ያሰኛል።

በመኪናው ሞተርና ውስጣዊ አሰራር ላይ በኢንጂነሩ የተወሰዱት ቀጣይ ምርመራዎች የችግሩን መንስኤ ፍንትው አድርገው አወጡት፤ ይኸውም በነዳጅ ስርጭት መቆጣጠርያ አካል ውስጥ በእመቃ የሚፈጠርን ትነት የሚዘጋና የሚከፍተው ክፍል ("vapor lock") በትክክል አለመስራቱ ነበር። ደንበኛው በየእለቱ ወደ ጣፋጭ መሸጫው ይሄዳል፤ መኪናውን አቁሞ ሌሎቹን አይነት ጣእሞች ገዝቶ ሲመለስ ቆየት ስለሚልና ሞተሩ ጊዜ ወስዶ ስለሚቀዘቅዝ በቀላሉ ይነሳል፣ የቫኒላ ጊዜ ግን ቶሎ ሲመለስ የመኪናው "ትነት መቆጣጠርያ" በትክክል ስለማይሰራና ሞተሩ በአግባቡ እንዳይበርድ ስለሚያደርገው አይነሳም።

እክሉ ከስር ተመርምሮ መፍትሄው ተገኘ። አንጋፋው የአለማችን ኩባንያ ጄኔራል ሞተርስ ብቃት ያለው አመራርና ሠራተኛ የአንድ ደንበኛውን ችግር ለመፍታት በሄደበት መንገድ ለኩባንያው የረጅም ጊዜ አገልግሎት የሚጠቅም ግኝት ተቀዳጀ። ልብ በሉ !

ለደንበኞቻችን ቅሬታ ጆሮ ከሰጠን፣ የማይረቡና የእብድ ሃሳብ የመሰሉ ችግሮችን እንኳን ሳንንቅና ሳናጣጥል በረጋ መንፈስ ካየናቸው፣ መፍትሄ ያገኙ ዘንድም ከተጋን ችግሮች ሁሉ እንደዚህ ቀላልና ለብዙሃን የሚበጁ ውጤቶችን ሊያቋድሱን ይችላሉ።

"አይቻልም" ከማለታችን በፊት በቀና መንፈስ በብርቱ ጥረት እንሞክረው።

"አ **<u>ይሞከር</u>** ም" ፣ አ **<u>ይደረግ</u>** ም" ፣ "አ **<u>ይቻል</u>** ም" · · · ·

ልብ በሉ፡- የቃላቱ የመጀመሪያና የመጨረሻ ፊደላት "አ" እና "ም" አፍራሽ ናቸውና ብናስቀራቸው የቀሩት ቃላት

**<u>ይሞከር</u>** ፣ **<u>ይደረግ</u>** ፣ **<u>ይቻል</u>** የሚሉ ይሆናሉ። እናም **እንሞክር ፣ እናድርግ . . . ይቻላል !።**

ከዚህ አንፃር እኛ ስለ ንግድና የአገልግሎት ህግ ያለን ግንዛቤ፣ ሙብትና ግዴታን የምናይበት ሚዛን፣ ለደንበኞች የምንሰጠው ክብርና መስተንግዶ ምን ይመስላል ብዬ ለማየት ሞከርኩና ማሰቤ በራሱ አሳቀቀኝ። ምክንያቱም አገልግሎት ሰጪና ተቀባይ፣ ሻጭና ገዢ፣ ገበያና ገበያተኛ እርስ በእርስ ያላቸው መተሳሰብ ባህላዊ እሴቱን እንኳ ወርውሮ በአንድ ጀምበር የመበልፀግ ልክፍት ሲያንደረድረው፣ የገዛ ወገኑን ርህራሄ ባልጎበኘው የዋጋ ንረት ሲያሸውና በማይመጥን ሸቀጥ ጥሪቱን ባደባባይ ሲዘርፈው፣ በማናለብኝ ንቀት ተገቢውን ክብር ሲነፍገውና አማራጭ አሳጥቶ ራሱን ተገልጋዩ ላይ ሲሾም ሳይ ጉዳዩን ሳልጀምረው ያስፈራኛል።

እውን ምን እየሆንን ነው? ደንበኛ በገንዘቡ ያሻውን አማርጦ እንዲገዛ ከማመቻቸት አንስቶ ድህረ ሽያጭ እስከሚያስፈልገው የዋስትናና ልዩ ልዩ አገልግሎቶች ድረስ የሚደረግ ግንኙነት፤ ብትፈልግ ግዛ ባትፈልግ ገደል ግባ እየሆነ ከዛሬ ነገ ሲብስበት፣ እያደር ሲነትብና አዘቅዝቆ ሲወርድ፣ አሁን ያለበት አሳፋሪ ደረጃ ላይ ደርሷል፤ እስከየት ሰምጦ መቆም እንዳለበት ግን ማናችንም የምናውቀው ነገር የለም። ይሄም አለ! በተለይ አንጀታችንን የምታሳርሩት አንዳንድ የተሸከርካሪ ጥገና (ጋራዦች) እና ባለሞያዎች (መካኒኮች) ከዚህ ምን አስተዋላችሁ? . . . ብዙ የምትማሩት ያለ ይመስለኛል፡፡

ምንጭ - 100 Moral Stories – by Akramulla Syed
መጋቢት - 2006 - አዲስ አበባ



## በፍጹም ተስፋ አትቁረጥ !

ከእለታት በአንዱ ቀን የገበሬው አህያ በድንገት ጉድጓድ ውስጥ ገባበት። ገበሬው ተደናገጠ፣ እንዴት አድርጎ ከጉድጓዱ እንደሚያወጣው ግራ ተጋባ። ጉድጓዱ ቀደም ባለ ጊዜ ለውሃ ተቆፍሮ ያለአገልግሎት የተቀመጠና እጅግ ያረጀ በመሆኑ አህያውን ለማውጣት በሚደረግ ማናቸውም ሙከራ ግድግዳው ሊናድና በሰው ላይ የከፋ አደጋ ሊያደርስ ስለሚችል አህያውን የማትረፉ እድል ጠባብ ሆነ።

አህያው የሚያሰማው ማቃሰትና የጣር ጩኸት ከጉድጓዱ አልፎ በርቀት ይሰማ ነበር። ጎረቤቶቹ አንድ አንድ እያሉ መምጣት ጀመሩ የቀሩትንም ይረዱት ዘንድ ጠራቸው። እንዲህ እንዲያ እያሉ መከሩ። የአህያው እርጅና ከጉድጓዱ አስጊነት ጋር ተዳምሮ አህያውን ከስቃይ ለመገላገል ወዲያውም ከሌላ መሰል አደጋ ለመዳን ሲባል ጉድጓዱን በአፈር ለመድፈን ውሳኔ ላይ ተደረሰ።

ጉድጓዱን የመሙላቱ ሥራ ተጀመረና . . . ጉብታው እየተቆፈረ አፈሩ በአካፋ ወደ ጉድጓዱ ይወረወራል። በመጀመሪያ አፈሩ ላዩ ላይ ሲበተን አህያው በመፍጨርጨር ከፍተኛ የድረሱልኝ ጩኸት አሰማና ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ ግን ፀጥ አለ። ሁኔታውን ለማጣራት ወደ ጉድጓዱ አፍ የተጠጋው ገበሬ ያየውን ማመን አልቻለም። አህያው በፍፁም ቅልጥፍና አስደናቂ ተግባር በመፈፀም ተጠምዷል። ጀርባው ላይ የሚያርፈውን አፈር በፍጥነት እያራገፈ እግሮቹን በማንቀሳቀስ አፈሩ ላይ ያውላቸዋል። በአካፋ እየተዛቀ ወደ ጉድጓዱ የሚረጨው አፈር እየጨመረ ሄደ። አህያውም ከእያንዳንዱ አካፋ የሚወርድበትን አፈር ከላዩ እያራገፈ አንድ ደረጃ ወደ ላይ ከፍ ይላል።

ገበሬውና ጎረቤቶቹ ይህንን አስገራሚ ተግባር እያደነቁ ፍፃሜውን ለማየት በጉጉት ጉድጓዱን ለመሙላት መረባረባቸውን ቀጠሉ። ጥቂት ቆይቶ ከጉድጓዱ አፍ አህያው ብቅ አለ በመጨረሻም ጠርዙ ላይ ሲደርስ በቀላሉ እንጣጥ ብሎ በመውጣት ከሰዎቹ ጋር ተቀላቀለ ። ይባላል።

ህይወት በየቀኑ አካፋ ሙሉ ቆሻሻ በላያችን ላይ ትዘረግፋለች።  የቆሻሻው አይነትና የአካፋው መጠን እንደ እያንዳንዳችን ውሎ ይለያይ እንጂ በየጊዜው ከሚገጥመንና ከሚነሰነስብን የችግር ናዳ የምንድነው እንደ አህያው ከላያችን ላይ አራግፈን፤ በዘዴና በጥረት አንድ ደረጃ ከፍ ብለን ላዩ ላይ ስንቆም ብቻ ነው። የኑሮ ፈተና ይገጥመናል፣ መሰናክሎች ይጋረጡብናል፣ ተደራራቢ ችግሮችና ምስቅልቅል ሁኔታዎች ይከቡናል፤ የመከራ ጥልቅ ጉድጓድ ውስጥ ብንወድቅ እንኳ ለአፍታም ባለመቆም፣ የተበተበንን የሴራ ወጥመድ ያለመታከት በመበጣጠስና የሚነሰነስብንን እኩይ ውርጅብኝ ከላያችን ላይ በማራገፍ፤ ፍጹም ተስፋ ሳንቆርጥ በመራመድ ብቻ ልንወጣው ይቻለናል!። በእርግጥም እንችላለን!። አህያ እያልን በንቀት የምንጠራውና የድድብና ተምሳሌት ያደረግነው እንስሳም ያሳየን ይህንኑ ነው።

ምን ጊዜም አምስቱን በደስተኛነት የመኖር ቀላል መርሆች እናስታውስ :-

❶· ልቦቻችን ከ ጥላቻ ይጽዱ ❷ · ጭንቀትን ከ አእምሯችን እናስወግድ
❸· ኑሯችን ቀለል ያለ ይሁን
❹ · ብዙ እንስጥ ❺ · ጥቂት እንጠብቅ።

ምንጭ፡ የሥነ ምግባር ትምህርትና መሳጭ ታሪኮች ስብስብ ድረ ገጽ
Swayamsat Meet Yourself (Institute of Clinical Hypnosis and Related Sciences PLC)
ጥቅምት - 2006 - አዲስ አበባ




## "የ ዛሬ . . . ነገ . . . ጦስ"

እለቱ የጋብቻቸው አሥረኛ ዓመት በአል የሚከበርበት ልዩ ቀን ነው። አይሻ ሰዓቱ አልሄድ ብሏት፣ ረጅም መንገድ ተጉዞ የሚመጣ ባሏን በመጠበቅ በር በሩን እያየች የምትለውን ታብሰለስላለች። ጊዜው ተቀይሯል፤ ለደቂቃ ተለያይተው መቆየት የማይችሉት ጥንዶች እንደዛ ጣፋጭ የነበረ ፍቅራቸው መምረር ከጀመረ ከራርሟል፤ ዛሬ ግን መለወጡን ልታሳየው ጓጉታለች።

በትንሽ በትልቁ ይነታረካሉ፣ የሚለው አይጥማትም፣ የምታደርገውን በጥሩ መንፈስ የሚቀበለው አይመስላትም። ጭቅጭቅ በነገሰበት ጎጆ ሰላም ሰፍኖ ትዳራቸው እንዲታደስ ታጋሽና ይቅር ባይ ለመሆን ከወሰነች ብትቆይም ዛሬ ነገ ስትል አልነገረችውም።

ባሏ ራጂብ የዛሬዋን ቀን ያስታውስ ይሆን? አይሻ ይህንን እያሰበች ጉድ ጉድ ስትል በሩ በለሆሳስ ተንኳኳ። ብ ር ር ብላ በሩን የከፈተችው አይሻ በቀኝ እጁ እቅፍ አበባ፣ በግራው ደግሞ የሻምፓኝ ጠርሙስ ይዞ ፊት ለፊት የቆመው ሰው ላይ ተጠመጠመች። በስስት አንገቱን፣ ከንፈሩን፣ ፊቱን እንዳገኘች ስትስም ክልብስ ባለው እንባዋ ታጅባ ነበር። ያሳለፉትን ክፉ ጊዜ ወዲያ ጥለው፣ ህይወትን እንደ አዲስ የሚያጣጥሙበት ቀን መጀመሩን ለማብሰር ከዚህ የተሻለ አጋጣሚ የለም። አሁን አሥር ሻማዎች ባደመቁት ሳሎን፤ የተዘጋጀውን እራት ቀማምሶ የሻምፓኙን ጽዋ ማንሳትና ዝግ ብሎ በሚንቆረቆረው ሙዚቃ መፍሰስ ነው። እደጅ ካፍያው ሃይሉን ጨምሮ መዝነብ ጀምሯል። አቤት! . . . ትክክለኛው . . . ሰዓት። ስልኳ ከመኝታ ቤት ጥሪ ሲያሰማ ፈጠን ብላ ወደዚያው ሄደችና አነሳችው።

"ሃሎ - ሃሎ" ደዋዩ ወንድ ነው።

"ጤና ይስጥልኝ የኔ እመቤት። የምደውለው ከፖሊስ ጣቢያ ነው። እባክዎን እርስዎ የአቶ ራጂብ ሜህራ ባለቤት ኖት?"

"አዎን ነኝ ። ምነው?"

"በጣም አዝናለሁ የኔ እመቤት። እዚህ አደጋ ተፈጥሮ የአንድ ሰው ህይወት አልፏል። ይህንን ቁጥር ያገኘነው የሟቹ የኪስ ቦርሳ ውስጥ በነበረው መታወቂያ ላይ ከሰፈረው የአደጋ ጊዜ ተጠሪ አድራሻ ሲሆን። እርስዎን የፈለግነውም መጥተው አስከሬኑን አይተው እንዲያረጋግጡልን ነው" አለ።

አይሻ ልቧ መምታቱን ያቆመ መሰላት!። ብርክ ያዛት፣ ተንቀጠቀጠች!። "ግን . . . ግንኮ ባሌ እዚህ ነው አለ . . . አለ ለ . . . " ተንተባተበች።

"አዝናለሁ የኔ እመቤት አደጋ ያጋጠመው ከአንድ ሰዓት በፊት ባቡር በመሳፈር ላይ ሳለ ነበር" አላት።

አይሻ ራስዋን ለመሳት ተቃረበች። በህልሜ ይሆን ያየሁት?። እንዴት ሊሆን ይችላል?።

በመጨረሻዋ ሰዓት የሚወዷቸውን ለመሰናበት ስለሚመጡ የሙት መንፈሶች የሰማችው ትዝ አላት። ስልኩን ጥላ ለማረጋገጥ እያደናቀፋት ወደ ሳሎን ሮጠች። ባሏ የለም። እግሯ መራመድ አቃተው በእንብርክክ ሌላው መኝታ ክፍል ገባች። እዛም የለም። "እውነት ነው! ተሰናብቶኝ ሄዷል! ላይመለስ ጥሎኝ አምልጧል። ፈጣሪ ሆይ መጨረሻ ላይ ባገኘሁት አጋጣሚ በየጥቃቅኑ ነገር እንደማልጨቀጭቀው ሳልነግረው ቀረሁ?። ባለቀ ሰአት በገጠመኝ አማራጭ እንኳን እንደምወደው ሳልገልጽለት አመለጠኝ!። ካልሞትኩ ዳግም ላላገኘው ነው? እያለች በፀፀት መሬቱ ላይ ወድቃ እየተንፈራፈረች ታለቅስ ጀመር . . .።

በድንገት መታጠብያ ክፍሉ ውስጥ ድምጽ ሰማች። ወዲያው ራጂብ በሩን ከፍቶ ወጣና "የኔ ውድ ባቡር ስሳፈር የኪስ ቦርሳየ መሰረቁን ሳልነግርሽ . . ." አላት። ማልቀሷን ሳታቋርጥ ቀና ብላ በስስት ዓይን ስታየው ከወደቀችበት ሊያነሳት ጎንበስ አለ . . . ተቃቀፉ። ይኸው ነው።

ልብ በሉ! ህይወት ግን የዚህ አይነት ሁለተኛ አማራጭ አትሰጠንም። ይህን መሳይ በድጋሚ የሚገኝ አጋጣሚም ከቶ የማይታሰብ ነው። እነሆ :- ስህተታችንን ለማረም፣ ስሜታችንን ለመግለጽና የውስጣችንን ለማውጣት በምንም አይነት ጥቂት ሰከንዶችንም ቢሆን ማባከን እንደማይገባን ታሪኩ በቂ ትምህርት ፈንጥቆልናል።

እስቲ ይህችን ጉዳይ ከማህበረ ሰባችን አንፃር አስምረን እንያት። ይህንን ጽሁፍ ሳዘጋጅ አንድ ከረጅም ጊዜ በኋላ የገኘሁት የልጅነት ጓደኛዬ ያጫወተኝ በራሱ ላይ የተፈፀመ ታሪክ ትዝ አለኝ። ነገሩ እንደዚህ ነው የጓደኛዬ አባት ባደግንባት ከተማ አሉ የተባሉ ሃብታም የቡና ነጋዴ ነበሩ። እነህ ታታሪ አባት ከስኬታቸው ባሻገር የቤተሰብ አስተዳደራቸው እጅግ ጥብቅና ጠንካራ እንደነበር ልጆች ሳለን ከኛ ጋር ለመጫወት የሚፈጥራቸው ሰበቦችና ሲያረፍድ የሚፈጠርበት ስጋት አይረሳኝም። ቤተሰቡ ምንም ሳይጎልበት በምቾት ቢኖርም ስለ አባታቸው የንግድ እንቅስቃሴ ግን የሚያውቀው ኢምንት ነበር።

በዚህ አይነት ሲኖሩ ቆይተው ከእለታት በአንዱ ቀን አባት ሥራ ላይ እንዳሉ ድንገት ራሳቸውን ስተው በመውደቃቸው ምክንያት ወደ ጤና ጣብያ እንደተወሰዱ ተነገራቸው። ፈጥነው ጤና ጣብያ የደረሱት የቤተሰቡ አባላት ያገኟቸው አባ ወራ መናገርም ሆነ ከተወሰነ የአካል ክፍሎቻቸው በስተቀር ማንቀሳቀስ አይችሉም ነበር። ጓደኛዬ በፀፀት ስላባቱ ሲነግረኝ “በጤና ጣብያ ቆይታው፣ በኋላም ወደ ሌላ ህክምና ማእከል ከተዛወረ በኋላ አንድ ነገር መናገር እንደፈለገ በምልክት ይጣራና ምንም ነገር መናገር ባለመቻላሉ የሚሰማውን ቁጭት ከአይኑ እንረዳ ነበር። እንደምታውቀው የንግዱ ባህሪይ በየቀኑ ለቡና ግዢ በርካታ ገንዘብ ከማንቀሳቀሱ አንፃር ዘመናዊ የሂሳብ አያያዝ አልነበረም። ግፋ ቢል ከመዝገብና ከመተማመን ውጪ አብዛኛውን ነገር በአእምሮው ያሰላ ስለነበር መናገር የሚፈልጋቸው ብዙ ጉዳዮች እንደነበሩ አያጠራጥርም። ምን ያደርጋል አንዳችም ቃል ሳይተነፍስ ለቀናት ተሰቃይቶ አረፈ። እኛም ብዙ ገንዘብ ወጥቶ እንደቀረ እያወቅን ከመዝገብ ከማስታዎሻዎችና አምነው ከመለሱልን ሰዎች ያገኘናትን ሰባስበን ዝም አልን” በማለት ከነገረኝ ገጠመኙ ጋር የሚቀራረብም ሆነ የሚመስል ታሪክ በየጎጀው እንደሚኖር ገመትሁ።

ወደ ወጋችን መነሻና ዋና መልእክት ስንመለስ በምስጢር መያዝ ያለባቸው ነገሮች እንዳሉ ሁሉ፤ መገለጽ ያለባቸው በርካታ ጉዳዮች በጊዜ ሳይነገሩና በዛሬ ነገ ሳይተላለፉ ተቀብረው የሚቀሩበት አጋጣሚ ብዙ ነው። ከግል መልእክት አንስቶ ኑዛዜና ንስሃዎች፣ ከአደራ ከምስጋናና ከልዩልዩ በረከቶች አንስቶ እስከ ብርቱ የጥቆማ ፈለጎችና ፍቱን የመድሃኒት ግኝቶች ድረስ በርካታ እጅግ ጠቃሚ ውጤቶች ከባለቤቶቻቸው ጋር ለዘላለም ተቀብረዋል።

ለምን? በሥመ ምስጢር ድብቅነታችን በሚፈጥራቸው ስጋቶች የተነሳ ውስጣዊ ስሜታችንን ለመግለጽ ጊዜ ስለምናባክን አልያም ጭራሹኑ ዝም ስለምንል . . . ይሆናል። ከዚህ ቀደም ከየት እንዳነበብኳት የጠፋችኝ አንድ ጥቅስ “በማንኛውም ጊዜ ልናደርግ የምንችለውን ነገር ምን ጊዜም ላናደርገው እንችላለን" ትላለች፤ አይመስልም?።

እስቲ ደግሞ ጥቂት ገባ ብለን የኛን ባህሪይና የግልጽነትን ጉዳይ እንይ . . . ሃበሾች ስሜታችንን በመግለጽ በኩል ያለብንን ድክመት የውጭም የኛም ሰዎች ደጋግመው ነግረውናል። ስለምን ልዝብ ሆንን? ለምን የምናስበውን በቀጥታ የማናንፀባርቅ ድብቆች ሆንን?። የውስጣችንን እውነት በአንደበታችን ወይም በድርጊታችን የመግለጽ ብቃት የሚጎድለንስ ለምንድነው?። ውስጣችን እያዘነ ደስተኛነታችንን እንገልፃለን፣ እያመመን በጎ ነን እንላለን፣ ጣራ በነካ ተጽእኖ ስር ሆነን ስለ ነፃነታችን እንለፍፋለን፣ ወድቀን እየተንከባለልን በጥንካሬ ስለመራመዳችን እናወራለን። እያቃጠለን - ቀዘቀዘን፣ ብርድ እያንዘፈዘፈን - ወበቅ ለበለበን በማለት ስር በሰደደ የማስመሰል ደዌ ለዘመናት መጠቃታችን አልታወቀንም ወይም አውቀን እንዳላወቅን እየሆንን ነው። ይህ ከሃሜት የዘለለ እውነት የማያሻማ መልስ ይፈልጋል። በመስኩ የካበተ ልምድና የትንተና ብቃት ያላቸው ምሁራን የሚያቀርቡትን የጥናት ውጤት ለማየት ብንበቃ ምንኛ መታደል ነበር ። (እንደ ጥቆማ ትያዝልኝ)።

“ማንም ሰው ነገን መተንበይ አይችልምና ራሳችንን ለይቅርታ እናዘጋጅ !"
"ማድረግና ማለት ላሉብን ነገሮች ጊዜ ሳንሰጥ - ወዲያው እንጀምር !"
"ውስጣችንን ለመግለጽ (“አካፋን - አካፋ") የማለት ወኔ ይኑረን !"

ደራሲ፡ ያልታወቀ
ምንጭ፡ የሥነ ምግባር ጽሁፎች ስብስብ ድረ ገጽ by Alina Dmitrenko

**"VALUE RELATIONSHIPS IN TIME BEFORE YOU REALIZE AND THE TIME IS TOO LATE"**

ጥር - 2006 *** አዲስ አበባ

## "እርግጠኝነት"

ከእለታት አንድ ቀን የእንቁራሪቶች ውድድር ተደርጎ ነበር። ውድድሩ ከተማው መሃል የሚገኝን አንድ ትልቅ ባለ አስር ፎቅ ሕንፃ እስከ ጫፍ ወጥቶ ማጠናቀቅ ሲሆን በርካታ ወጣት እንቁራሪት አትሌቶች ተሰልፈዋል። ሥፍራው ይህንኑ ውድድር ለመከታተልና ተሳታፊዎቹን ለማበረታታት ከተለያየ ቦታ በተሰባሰቡ ሰዎች ተጨናንቋል።

ከየአቅጣጫው ልዩ ልዩ ቃላቶች ይሰነዘራሉ አንዱ "አይይ – ከንቱ ድካም! ፎቁ በጣም ረጅም ነው፤ በፍጹም የሚሞከር አይደለም" ሲል፣ ሌላው ደግሞ "አሁን እነዚህ ናቸው ይህን ቀጥ ያለ ፎቅ ወደ ላይ የሚወጡት? እብደት ነው! ቢቀርባቸውስ" እያለ የውድድሩን አደገኛነትና የእንቁራሪቶቹን ደካማነት በማጉላት አስተያየቱን ይሰነዝራል።

የማስጀመሪያው ሽጉጥ ተተኮሰ . . . እውነቱን ለመናገር ከተመልከቹ መሃከል ማንም ሰው እነዚህ እንቁራሪቶች ጥቂት ሜትሮች እንኳ ችለው ይዘላሉ ብሎ ያሰበ አልነበረም። ከሶስተኛው ፎቅ በኋላ እጅብ ብለው የሚሮጡት እንቁራሪቶች በተንተን እያሉ በመካከላቸው ያለው ርቀት እየሰፋ መጣ፤ አንዳንድ እንቁራሪቶች መውደቅ ጀመሩ። ተመልካቹ "ይኸውና ያልነው አልቀረም! አይችሉትም፣ ወድቀው ማለቃቸው ነው" እያለ ይጮሃል። ወደ ፊት ከቀደሙ ጥቂት ተወዳዳሪዎች በስተቀር፣ ደከሚቸው የሚቆሙና ውድሩን አቋርጠው የሚወጡት እየበዙ ሄዱ። ህዝቡ አሁንም ይጮሃል "በቃ – አለቀላቸው፣ ማንም ችሎ አይጨርስም . . ." ይላል። አንድ በአንድ እየተንጠባጠቡ በመጨረሻ አንዲት ወጣት እንቁራሪት ቀረች። ይህችው እንቁራሪት አትሌት በብቸኝነት እየመራች ቆይታ የፎቁን ጫፍ በመውጣት የአሸናፊነቱን ድል ተቀዳጀች።

አብዛኛዎቹ ያጡትና አሸናፊዋ እንቁራሪት የተላበሰችው የጥንካሬ ምስጢር ከቶ ምን ሊሆን እንደሚችል መገመት አልተቻለም። ተወዳዳሪዎቹም ተመልካቹም በአድናቆት ተደሞ እያለ ጋዜጠኛው ወደ አሸናፊዋ አትሌት ተጠጋና ጠየቃት "የአሸናፊነት ምስጢርሽ ምንድን ነው?"

መልስ ልትሰጠው አልቻለችም፣ ግራ ተጋብታ ቆየችና በምልክት አስረዳችው። ምስጢሩ ታወቀ! . . . እንቁራሪቷ መስማት አትችልም – <u>ደንቆሮ</u> ናት።

ሌሎቹ መወዳደራቸውን እንጂ ለማሸነፍ ያላቸውን ብቃት በወጉ አልተማመኑበትም። በተለይ ከውጭ የሚሰነዘረውን ተቃራኒ አስተያየትና አፍራሽ ሃሳብ መቋቋም ስለተሳናቸው መቀጠል አቅቷቸው እየወደቁ ቀሩ። አጉል የሚሰነዘር ትችትና ዝቅተኛ ግምት፤ ተስፋ ያስቆርጣል፣ በራስ መተማመንን ይሸረሽራል፣ የተወዳዳሪነትንና አሸንፎ የመውጣትን አቅም ፈተና ውስጥ ይጥላል፣ ብሎም ሳይጀምሩ ወደ መፍረክረክና አቋርጦ በመውጣት እስከመሸነፍ ያደርሳል።

ወዳጆቼ ልብ በሉ! ለውድቀት የሚዳርጉት ተቃራኒና አፍራሽ አስተያየቶች ብቻ አይደሉም። ከዚህ ባልተናነሰ እንደውም በበለጠ ሁኔታ የተጋነነ ድጋፍና ሙገሳ፣ መጠን ያለፈ ውዳሴና ከአንተ በላይ ለአሳር ቁልምጫ፤ ብዙዎችን ከመስመር እያስወጣና ካሰቡበት ወዲህ ተጨናግፈው እንዲቀሩ ዋና ምክንያት ሲሆን እያየን ነው።

እንቁራሪቷ የተመልካቹን አፍራሽ ትችት ስላልሰማች . . . አለመስማቷ በዚህ ውድድር ተስፋ ሳትቆርጥ እስከመጨረሻው ትፋለም ዘንድ ረድቷታል ማለት ይቻላል። ይህ ማለት አለመስማቷ፤ እንደ መፍትሄ ለሌላ ውድድር ማሸነፍያ ይሆናታል ማለት ግን አይደለም። ምክንያቱም በውድድሩ ወቅት ከፊት ለፊት የተከሰተ አደጋን ወይም ማዳመጥን ግድ የሚል ሁኔታን መቋቋም ስለማትችልና ድንቁርና ሁሌም የማሸነፍ ጽናት ተደርጎ እንዳይታሰብ ለመጠቆም ነው።

የታሪኩ አብይ መልእክት ፡- ህይወት የውድድር መድረክ ናት። እኛ ደግሞ የእለት ተእለት ኑሮና ህልማችንን ለማሳካት፣ የአጭርና የረጅም ጊዜ እቅዳችንን በብቃት ለመወጣት ሠርክ የምንታትር አትሌቶች ነን። የዚህ ውድድር ልዩነቱ ማሸነፍና መሸነፍ (ስኬትና ውድቀት) እንጂ እኩል ለእኩል ወይም ዜሮ ለ ዜሮ ብሎ ነገር የለበትም። በሦስት አይነት ተመልካቾች ተከበናል። አንዱ አቅማችንን አኮስሶና ችሎታችንን ንቆ የውድድሩን ሃያልነት እጅግ በማጉላት ከቶም እንደማንወጣው ይለፍፋል። ይህንን ተስፋ አስቆራጭ ታዳሚ የአሰናካይ ስብስብ እንበለው። ሁለተኛው ተመልካች በትክክል የሚታይብንን ድክመት በቅን ህሊና የሚጠቁምና የማሸነፍያ ጥበባትን የሚያመላክት ስለሆነ ይህ ምድብ – ምክረ ቢባል ይገባዋል። ሦስተኛው ወገን የሌለንን እየቆለለ፣ ባልዋልንበት እየካበ፣ ዝናና ተሰጧችንን ከጣራ በላይ ሰቅሎ የውድድሩን ኢምንትነት የሚያውጅ፣ ስብእናችንን እስክንጠራጠር እያሞካሸ በአጉል ተስፋ የሚያሞግሰን በመሆኑ – አጉሌ ቢባልስ?።

ተመልካቹ ይጮሃል፣ ያሻውን ይሰነዝራል – አጉሌዎች ያዳምቃሉ፣ አሰናካዮች ያሳቅቃሉ፣ የኑሮ ግብ ግብ መስክ፣ የህይወት ፍትጊያ ሜዳ በዝብርቅርቅ ድምፀት ተሞልቷል። ቅን አሳቢዎቹ እነምክረ ዛሬ ዛሬ ጠፍተዋል አይገኙም። የኛን ሜዳ የሞሉት፣ እንደ አሸን የፈሉትና በእጅጉ የሚያዘወትሩት ታዳሚዎች ሌሎቹ ናቸው። (እነ ሳንካውና አጉሌ)

ግማሾቹ ተስፋ ቆርጠን ሳንጀምር እንድንፈራ፣ ሳንሞክር እንድናቋርጥ ይገፉናል። ውስጣዊ ስሜታችንን አላሽቀውና ወኔአችንን ሰልበው ለተሸናፊነት ያጨናል። ሌሎቹ ደግሞ ከአቅማችን በላይ ይክቡናል፣ በቀላሉ እንደምናልፍና ለድል እንደምንበቃ በአጉል ድፍረት እንድንኮፈስና ውሎ ሲያድር በሽንፈት አንገታችንን እንድንደፋ ያመቻቹናል። ሁሉም ይጮሃሉ! ሆ! ሆ! ሆይ! . . . ይላሉ - በገሃዱ አለም።

ይሄኔ እንደ እንቁራሪቷ ደንቆሮ ሆነን ሁሉንም ባንሰማ ይመረጣል፡፡ እኛ ግን መስማት እንችላለን፡፡ ሰምተን አለማዳመጥም እንችላለን፣ በጎውን ከክፉ ለይተን የፈለግነውን ብቻ መቀበል፣ ያልጣመንንና የማይበጀንን እንዳልሰማን መቁጠር እንችላለን፣ ሁሉን ትተን ውስጣችንን ብቻ ማዳመጥም እንችላለን፡፡ እየሰሙ አለማዳመጥ ይኸው ነው፡፡ እስከ መጨረሻው መስመር ለመታገልና የፍፃሜዋን ጥብጣብ በድል በጥሶ ለመግባት ብቸኛው ጎዳና፤ አንድና አንዱ አማራጭም ይኸው ነው፡፡ ራሳችንን ሆነን፣ ከህሊናችን ጋር አብረን፣ በብቃታችን ተማምነንና ማሸነፋችንን ብቻ አልመን መፋለም፡፡ ምንግዜም ቀና ብሎ በራስ መተማመን፤ እርግጠኛነት ማለትም ይኸው ነው፡፡

ምንጭ ፡ www.RogerDarlington's World
"Always stay... POSITIVE"
ታኅሳስ - 2007 ዓ.ም.

## **"መስጠት"**

ዴቪድ እባላለሁ ፡-

ከብዙ አመታት በፊት በበጎ ፍቃደኛነት ለማገልገል ወደ አንድ ሆስፒታል ተልኬ ጥቂት ወራት ቆይቼ ነበር። ታዲያ በሆስፒታሉ የህመምተኛ ህፃናት ክፍል ውስጥ አንዲት ሊዛ የተባለች ህፃን በከፍተኛ ህመም ስትሰቃይ አይቼ፤ ሁኔታዋን ለማወቅ ባደረኩት ሙከራ የዚህች ህፃን ህይወት ሊተርፍ የሚችለው የስምንት አመት ልጅ ከሆነው ወንድሟ በሚወሰደው ደም ብቻ እንደሆነ የሚከታተላት ሃኪም ነገረኝ፡፡ ምክንያቱም ወንድሟ ተዓምር ሊባል በሚችል ሁኔታ በተመሳሳይ በሽታ ተጠቅቶ መዳን በመቻሉና የሱ ደም ይህን በሽታ የመቋቋም አቅሙን ስላጎለበተ ብቸኛው መፍትሄ ይኸው ብቻ ነበር። የህክምና ቡድኑ ተገቢውን ምርመራ አጠናቆ እንደጨረሰ ሁኔታውን ለልጁ ቤተሰቦች ለማስረዳት ተስማማ።

ከዚያም አንደኛው ዶክተር ከህፃኑ ወላጆች ጋር ከተነጋገሩ በኋላ ወደ ልጁ ቀርበው ለእህቱ ህይወት መትረፍ የእሱ ደም አስፈላጊ እንደሆነና ደሙን ለመስጠት ፍቃደኛ መሆኑን ጠየቁት?። ህፃኑ ያለምንም ማመንታት "አዎ የእሷን ህይወት የሚያተርፍ ከሆነ አሰጣታለሁ" አለ፡፡ ይህ ህፃን በልበ ሙሉነት ሲናገር ስሰማ በእውነቱ በጣም ተገረምኩ፡፡

በቀጣዩ ቀን አስፈላጊው ዝግጅት ተጠናቆ፣ ወንድምና እህት ጎን ለጎን ተኝተው፣ ደም የማስተላለፉ ስራ እንደተጀመረ ትንሹ ልጅ አመድ የመሰለው የእህቱ ፊት እየወዛ ሲመጣ አይቶ ተደሰተ። ወደ ዶክተሩ ዞር ብሎም "እሷ እየተሻላት ነው፣ እኔ ደግሞ መቼ ነው መሞት የምጀምረው? ገና ነው?" በማለት ጠየቃቸው።

ይሄኔ ዶክተሩ ህፃኑ ልጅ ሁኔታውን እንዳልተረዳው አወቁ። ለካስ ህፃኑ የመሰለው፤ የእሱ ደም ሙሉ በሙሉ ተወስዶ ለእህቱ ሊሰጥና እሷ ድና እሱ እንደሚሞት ነበር። ይሄኔ ሁላችንንም አስገረመን፣ ልባችንን ይበልጥ ነካው። በዚህ እድሜ ፍቅሩን እስከ መጨረሻው በመስጠት እህቱን አድኖ ራሱ ሊሞት ወስኖ ነበር፡፡ ድንቅ ነው! እህቱ እስካዳነች ድረስ ደም ለሱ ምንድነው? ህይወትስ?።

እኛስ ምን ለመስጠት ተዘጋጅተን ይሆን? - ፈገግታም መስጠት ነው፣ ሰላምታም መስጠት ነው፣ ይቅርታም፣ ገንዘብም፣ ደስታም መስጠት ናቸው። ያለስስት መስጠትስ?። በአይኔ ያየሁት ይህ አጋጣሚ ስለ መስጠትና ልግስና ባሰብኩ ቁጥር ከህሊናየ ሳይጠፋ አብሮኝ ይኖራል። በማለት ዴቪድ ገጠመኙን ደመደመ።

እውነቱን ለመናገር እኛ ለመስጠት አልተዘጋጀንም!። ህፃኑ ልጅ ግን አድርጎታል፣ ሳያቅማማ በመስጠት ፈጽሞታል። ፍቅር እስከዚህ ድረስ እንደሚሄድ አበክሮ አሳይቷል። እስቲ ወደ ራሳችን ዞረን ውስጣችንን እንይ?

<u>እኛ ! ስለመስጠት እንዴት ነን ?</u>

<u>እኛ ! - ከመስጠታችን በፊት የምናገኘውን እናሰላለን፣ . . . በተቻለን ሁሉ ከምንሰጠው የበለጠ ለመውሰድ እናቅዳለን።</u>

<u>እኛ ! - የምንቀበለው ከምንሰጠው እንዲመጣጠን፣ . . . በብድርና ውለታ ስንኝ ክፍተቱን ለመሙላት እንተጋለን።</u>

<u>እኛ ! - በመቀበል አባዜ ናውዘን፣ ባልተፃፈ ሕግ ተስማምተን፣ . . . . ሲጀመር ጥቅም ካላገኘን ስለ መስጠት አናስብም።</u>

<u>እኛ ! - ሰጠን ከተባለ የማንፈልገውን እንጂ፣ . . . የሚፈለገውን መች ሰጥተን እናውቃለን?።</u>

<u>እኛ ! - በምጽዋት ሰበብ ሽርፍራፊ ሣንቲምና ቁራሽ ከምንጥልላቸው . . . . ነዳያን እንኳ ምርቃት አሰፍስፈን እንጠብቃለን።</u>

<u>እኛኮ ! - ምንም ካላገኘን ምንም ስለማንሰጥ መጽውተን ባልመረቁን . . . . የኔ ቢጤዎች ላይ - ፊታችንን የምናከፋ . . . ንፉጎች ነን።</u>

ወደድንም ጠላንም እኛ . . . እንደዚህና ከዚህም የባሰን ነን። ስለፍቅር እስከመጨረሻው መስጠትን ግን፤ ይኸው የስምንት አመቱ ህፃን እንዲህ አሳምሮ አሳየን። ቸሩ ፈጣሪ እድሜ ይስጠው። ለኛ ደግሞ ሩህ ሩህ ስብእናና አስተዋይ ህሊና።

አሜን !

ይህ ጽሁፍ አንድ ማኅበራዊ ድረ ገጽ ላይ ያገኘሁት ሲሆን
ገጠመኙን ያሰፈረው ሃኪም ሙሉ ስምና ቦታው አልተጠቀሰም።
መስከረም - 2008 ዓ. ም. - አዲስ አበባ

**<u>"እጅግ አስፈላጊ"</u>**




የፍልስፍና መምህሩ ፕሮፌሰር የተለያዩ ነገሮችን ጠረጴዛው ላይ አዘጋጅቶ ተማሪዎቹን በመጠባበቅ ላይ ነበር። ሁሉም እንደገቡ በቀጥታ የእለቱን ትምህርት መስጠት ጀመረ። አንድ ትልቅ ባዶ የከረሜላ ጠርሙስ በማንሳት ውስጡን በትንንሽ ድንጋዮች ሞላው።

ከዚያም ተማሪዎቹን ጠርሙሱ በድንጋይ መሞላቱን እንዲያረጋግጡ ከፍ አድርጎ አሳያቸው፤ እነሱም በትክክል እንደተሞላ አረጋገጡለት።



በመቀጠል ፓኬት ውስጥ የነበሩትን ጠጠሮች ጠርሙሱ ውስጥ ጨመራቸውና ጠርሙሱን በዝግታ ሲያነቃንቀው ጠጠሮቹ እየተንከባለሉ በድንጋይና ድንጋዮቹ መሃከል ባሉት ባዶ ቦታዎች ገቡ። አሁንም ተማሪዎቹን ጠርሙሱ መሞላቱን ጠየቃቸውና መሙላቱን አረጋገጡለት።



ፕሮፌሰሩ ጠረጴዛው ላይ የነበረውን ደቃቅ አሸዋ ጠርሙሱ ውስጥ ነሰነሰው፣ አሸዋው ጠርሙሱ ውስጥ የቀረውን ክፍት ቦታ ሁሉ ጥቅጥቅ አድርጎ ሞላው። ከዚያም "ተማሪዎች አሁንስ ጠርሙሱ ሙሉ ነውን?" ሲል ጠየቃቸው። በአንድ ቃል"አዎን መምህር ሙሉ ነው" በማለት መለሱለት።



በመጨረሻ ፕሮፌሰሩ ሁለት ሲኒ ቡና ከጠረጴዛው ላይ አንስቶ ጠርሙሱ ውስጥ ሲያፈስና ጥቁሩ ቡና የሞላውን ጠርሙስ ዙርያውን ሲያዳርስ ተማሪዎቹ በሳቅ አውካኩ። ፕሮፌሰሩም የሰርቶ ማሳያ ሙከራውን ጨረሰና "አሁን በጥሞና እንድትከታተሉኝ እፈልጋለሁ" በማለት የመልእክቱን ይዘት ያብራራ ጀመር።



"ይህ ጠርሙስ ፦ የእናንተን ሕይወት ይወክላል።

"<u>ድንጋዮቹ</u> ፦ እጅግ አስፈላጊ ነገሮች፣ ቤተሰቦቻችሁ፣ ልጆቻችሁ፣ ዘመድ - አጋሮቻችሁ፣ ጤንነታችሁ ባጠቃላይ ሁሉንም ነገሮች ብታጡ እንኳን እነሱ ካሉ ሕይወታችሁ ሙሉ እንደሆነ እንዲቀጥል የሚያደርጉ ዋና ዋና ነገሮችን ይወክላሉ።

<u>ጠጠሮቹ</u> ፦ ሌሎቹ ነገሮች ለምሳሌ እንደ ሥራችሁ፣ ቤታችሁ፣ መኪናችሁ . . . የመሳሰሉት ሲሆኑ።

<u>አሸዋው</u> ፦ የቀሩትን ጥቃቅን ነገሮችና የእለት ተእለት ጉዳዮች ይወክላል።"

"ልብ በሉ! በመጀመሪያ አሸዋውን ጠርሙሱ ውስጥ ብንሞላ - ለጠጠሩም ሆነ ለድንጋዩ የሚሆን ምንም ባዶ ቦታ አይኖርም። ይህ በሕይወታችሁ ውስጥም ተመሳሳይ ነው። መላ ጊዜአችሁንና ኃይላችሁን በጥቃቅኖቹ ነገሮች ላይ ካባከናችሁ ለሕይወታችሁ እጅግ አስፈላጊ ለሆኑት ነገሮች ምንም ቦታ አይኖራችሁም ማለት ነው። ቅድሚያ ለሕይወታችሁ መሰረታዊና እጅግ አስፈላጊ ለሆኑት ነገሮች ስጡ !።

መልካም ጊዜን ከትዳር አጋሮቻችሁ ጋር አሳልፉ፣ ከልጆቻችሁ ጋር ተጫወቱ፣ ከቤተሰቦቻችሁ ጋር ለመዝናናት ወጣ በሉ፣ ወደ ሥራ ለመሄድ ምን ጊዜም ሰአት አለ። በአንፃሩ ግን በቤታችሁ ውስጥ ከቤተሰቦቻችሁ ጋር የምታሳልፉትን የጊዜ መጠን በማስረዘም፣ ቤታችሁን በማጽዳትና የእቃ አቀማመጦችን በመቀያየር፣ የእግር ጉዞና የአካል ብቃት እንቅስቃሴዎችን በማድረግ ለጋራ ጤንነት ቦታ መስጠት። የእራት ግብዣ በማዘጋጀትና ማሕበራዊ ጉዳዮች ላይ በመሳተፍ አልያም የተበላሹ ቁሳቁሶችን በመጠገንና በመሳሰሉት ተግባራት እጅግ የላቀ ደስታን ተጎናፀፉ። ቅድሚያ ትኩረት፣ የበለጠ አስተውሎት በትክክልና እጅግ ለሚያስፈልጉን - ነገሮች እንስጥ - የተቀረው እንደ አሸዋው ነው፣ ቀስ ብሎ ይደርሳል።"

በዚህ መሃል አንዲት ተማሪ ጥያቄ ለመጠየቅ እጇን አወጣችና : "ቡናው ምንን ይወክላል?" ስትል ጠየቀችው።

ፕሮፌሰሩ ፈገግ ብሎ "ጥሩ ጥያቄ ነው፣ አስታውሰሽ ስለጠየቅሽኝ ደስ ብሎኛል። ይህ የተደረገው ሕይወታችሁ ምንም ያህል ጢም ብሎ የተሞላ ቢመስላችሁ፤ ምንጊዜም ከጓደኛ ጋር ፉት ለሚሉት ሁለት ሲኒ ቡና የሚሆን ቦታ እንደማይጠፋ ለማሳየት ነው" በማለት መለሰላቸው።

እውነት ነው! እስቲ ሁላችንም ዞር ብለን እናስተውል . . . ይእቺ ነገር በጨረፍታም ቢሆን ትመለከተናለች።

ደራሲ - ያልታወቀ
ምንጭ - ማሕበራዊ ድረ ገጽ INSPIRATIONAL and MORAL STORIES Collection
Motivation by STEPHEN - "The important things in life" ሰኔ 17 2005 ዓ. ም. * አዲስ አበባ

**"አስተዋይ ሁን !"**

ቻማን እና ጃጋን የዩኒቨርሲቲ ትምህርታቸውን ካጠናቀቁ በኋላ ሥራ በጀመሩበት አንድ የጅምላ ንግድ ኩባንያ ውስጥ በጠንካራ ሰራተኛነታቸው የሚታወቁ ነበሩ። ከዓመታት ቆይታ በኋላ የኩባንያው ዋና ስራ አስኪያጅ ጃጋንን ወደ ሽያጭ ክፍል ሃላፊነት ሲያሳድገው ቻማን ግን በነበረበት የሽያጭ ማስተባበርያ ዴስክ ንኡስ የሥራ ክፍል በመስራት ላይ ነበር። አንድ ቀን ቻማን ለኩባንያው ስራ አስኪያጅ የፃፈው ደብዳቤ የደረጃ እድገት ለመስጠት እርሳቸው የሚመለከቱት ታታሪ ሠራተኛነትን ሳይሆን ከንቱ ውዳሴንና ማስመሰልን በመሆኑ በኩባንያው ውስጥ መስራት ስለማይፈልግ ባስቸኳይ እንዲያሰናብቱት የሚጠይቅ ነበር።

ስራ አስኪያጁ ደብዳቤውን ፊት ለፊታቸው ጠረጴዛው ላይ እየተመለከቱ፤ ቻማን ብዙ ዓመታት ያገለገለ ጠንካራ ሠራተኛ ነው፣ አንድ እድል በመስጠት ልዩነታቸውን ያውቅ ዘንድ ብረዳውስ ሲሉ አሰቡ። ወዲያው ቻማንን ጠሩትና "ደብዳቤህን አይቸዋለሁ ከወዲሁ ግን አንድ ሥራ እንድታግዘኝ እፈልጋለሁ፤ ይኸውም ወደ ገበያው ሄደህ የሚሸጥ ሎሚ ካለ አጣርተህ እንድትመጣ ነው?" በማለት አዘዙት።

ቻማን ገበያ ደርሶ እንደተመለሰ "አዎን የሚሸጥ ሎሚ አለ" በማለት መለሰላቸው።

ስራ አስኪያጁም "የአንዱ ኪሎ ዋጋ ስንት ነው?" በማለት ጠየቁት።

ቻማን ዋጋውን ሊጠይቅ ወደ ገበያው ሄደ። ተመልሶ እንደመጣም "አንዱ ኪሎ 12 ብር ነው" በማለት ነገራቸው።

ስራ አስኪያጁ "በጣም ጥሩ አመሰግናለሁ! አንተ እዚሁ አረፍ በል፣ ጃጋንን ተመሳሳይ ሥራ አዘዋለሁ" በማለት ጃጋንን ጠርተው አዘዙት።

ጃጋን ገበያ ደርሶ እንደተመለሰ "የሚሸጥ ሎሚ ያለው አንድ ሰው ብቻ ነው፣ የአንዱ ኪሎ ዋጋ 12 ብር ሲሆን፣ 10 ኪሎ ለሚገዛ በቅናሽ 100 ብር ይሸጥለታል፣ ሻጩ በጠቅላላ 340 ሎሚዎች ሲኖሩት መደርደርያው ላይ ያሉት 58 ሎሚዎች እያንዳንዳቸው እስከ 200 ግራም የሚመዝኑና ከሁለት ቀን በፊት ከደቡብ የገቡ በጣም ጥሩ ጥራት ያላቸው ናቸው" በማለት መለሰላቸው።

በተመስጦ ያዳምጥ የነበርው ቻማን ደነገጠ!። የእርሱንና የጃጋንን ልዩነት ሲገነዘብ እፍረት እየተሰማው ወዲያውኑ አንድ ውሳኔ ላይ ደረሰ። እንዳቀረቀረ ከተቀመጠበት ተነስቶ ወደ አለቃው ተራመደና . . . "ስለሆነው ሁሉ አዝናለሁ! የመልቀቅ ሀሳቤን አንስቸዋለሁ፣ ከጃጋን በመማርም አገልግሎቴን መቀጠል እፈልጋለሁ" በማለት ውሳኔውን አሳውቆ በዝግታ እየተራመደ ክፍሉን ለቆ ወጣ።

እስቲ ራሳችንን እንመዝን - ጓደኞቻችንና የሥራ ባልደረቦቻችን ከፍ ሲሉ ወይም ከእኛ የተሻለ እድገት ሲያገኙ ወሬ ስለሚያቀብሉ፣ ዘመድ ስለሆኑ፣ መደለያ ስለሰጡ፣ ስለሚያስመስሉ አልያም ሰርቀው፣ አጭበርብረው፣ ቀጥፈው . . . ወዘተ በማለት ስንኮንንና ስናብጠለጥላቸው እንኖራለን? ወይስ የተሻሉ ስለሆኑ፣ ታታሪነታቸው ታይቶ፣ ብቃታቸው ተመዝኖ፣ አልያም በላባቸው፣ በጥረታቸው፣ በልፋታቸው . . . በማለት ከጠንካራ ጎናቸው ለመማር እንሞክራለን? ከየትኞቹ ነን?። በህይወታችን ምን ያህል አርቀን እናስባለን? ምን ያህል ጠልቀንስ ተገንዝበናል? የሚሉትን መሰረታዊ ነጥቦች መርሳት የለብንም። ብልህ፣ አስተዋይና አርቆ አሳቢነት በዘፈቀደ የሚታደሉት አይደለም፤ በጥረት፣ በቀና ህሊናና ሚዛናዊ አስተሳሰብ ውስጥ ተኮትኩቶ የሚያድግ፣ አብቦ የሚያፈራና በሂደት የሚፀና የልብ መርህ እንጂ አብረው የሚወለዱትም አይደለም።

ወዳጆቼ :- ስኬት የማስተዋል ረድኤት ነው። አስፍታችሁ አስቡ ፡ በጥልቀት ተረዱ። በየትኛውም መንገድ እጅጉን የተሳካለት ሰው በርካታ አመታትን አርቆ ያያል። እኛ ግን የነገን ብቻ እናያለን . . . አስቡት በአንድ ቀን እና በአንድ ዓመት መካከል ያለው ልዩነት ደግሞ 365 እጥፍ ነው።

ምንጭ :- 10 Greatest Stories Of All Time By Nicole H.
ጥር - 2007 ዓ.ም. አዲስ አበባ

<u>**"ምን ጊዜም አምላክህን አመስግን"**</u>

ይህ እውነተኛ ታሪክ ነው ፦



ሙሉ ሥሙ አርተር ሮበርት አሽ ይባላል - (እ.አ.አ.) ከ 1943 – 1993 የኖረ አሜሪካዊ ሲሆን የአለማችን ቁጥር 1 ፕሮፌሽናል የሜዳ ቴኒስ ተጫዋች፣ የመጀመሪያው አፍሪካ አሜሪካዊ በ ዊምብልደን በ ዩ ኤስና አውስትራሊያ ኦፕን - በሶስቱ ታላላቅ የሜዳ ቴኒስ ውድድሮች (3 Grand Slam Titles) አሸናፊ የነበረ ወጣት ነው።

አርተር አሽ ከፕሮፌሽናል የሜዳ ቴኒስ ተጫዋችነቱ ባሻገር በርካታ መጽሃፍትን ለአለም ያበረከተ፣ በጥቁሮች ላይ የሚፈፀሙ የዘርና የቀለም መድሎዎችን በመቃወም ሥመጥር ታጋይና ቀስቃሽ የነበረ ከመሆኑም በላይ በዚሁ ምክንያት ለእስር ተዳርጎ መከራውን ያየ ሰው ነው።

አርተር አሽ በስኬቶቹ መሃከል (እ.አ.አ.) በ1986 ገደማ የልብ ቀዶ ጥገና ሲደረግለት በተሰጠው ደም ምክንያት የ ኤች አይ ቪ ኤድስ ቫይረስ ተጠቂ ሆነ። ይህንኑ ይፋ ባደረገ ማግስት ከአለም ዙሪያ በ አስር ሺህዎች የሚቆጠሩ የማጽናኛና ማበረታቻ ደብዳቤዎች ደረሱት። ከደብዳቤዎቹ አንዷ እርሱ ከሰጠው መልስ ጋር እንዲህ ትነበባለች።

**<u>ደብዳቤ ቁጥር 4221</u>**

ይድረስ ለ አርተር ሮበርት አሽ - ዩ ኤስ ኤ
ስለደረሰብህ አስከፊ ሁኔታ በእጅጉ አዝናለሁ ።

**<u>ስለምን እግዚአብሄር ለዚህ መጥፎ በሽታ አንተን መረጠህ ?</u>**

ወዳጅህ ….
ከ ኬፕ ታውን - ደቡብ አፍሪካ

**<u>የ ደብዳቤው መልስ</u>**

ወንድሜ ! ስለፃፍክልኝ ደብዳቤ ከልብ አመሠግናለሁ።
ስለምን እግዚአብሄር ለዚህ መጥፎ በሽታ አንተን መረጠህ ? ለሚለው ጥያቄህ ግን - እነሆ። . . . በዓለማችን ላይ ፦
50 ሚሊዮን ህፃናት የሜዳ ቴኒስ መጫወት ይጀምራሉ።
5 ሚሊዮን ህፃናት ስለ ሜዳ ቴኒስ ጨዋታ የመማርን እድል ያገኛሉ።
500 ሺህ እድለኛ ህፃናት ፕሮፌሽናል የሜዳ ቴኒስ ስልጠና ያገኛሉ።
50 ሺህ በሜዳ ቴኒስ የውድድር ሰንጠረዥ ውስጥ ይገባሉ።
5 ሺህ በዓመታዊው የሜዳ ቴኒስ ውድድር ውስጥ ይካተታሉ።
50 በዊምብልደን የሜዳ ቴኒስ ውድድር ተካፋዮች ይሆናሉ።
4 ለግማሽ ፍፃሜ ይደርሳሉ።
2 የፍፃሜው ተጋጣሚዎች ይሆናሉ።
1 ብቻ በአሸናፊነት ያጠናቅቃል።

<u>ይህንን ሁሉ አልፌ፤ ታላቁን ዋንጫ ሳነሳ “እኔን ለምን መረጥከኝ” አላልኩም።</u>

ስለዚህ ዛሬም በህመሜ ውስጥ ሆኜ "እኔን ለምን መረጥከኝ" አልልም።
ቸሩ እግዚአብሄር ስላደረገልን 98 በመቶ ጥሩ ነገር ዘወትር ልናመሰግነው ይገባናል።

አመሰግናለሁ ። ያንተው አርተር ሮበርት አሽ

አርተር ሮበርት አሽ ፡- ነብሥህን በገነት ያኑረው፤ እኛንም ዘወትር . . . አመስጋኞች ያድርገን።

እውነተኛ ታሪክ - ከባለታሪኩ አርተር ሮበርት አሽ እለታዊ ማስታዎሻ የተወሰደ
ምንጭ፡- የዶክተር ሞሃመድ አብደልራህማን አል አሪፊ መጽሃፍ "ህይወትና ደስታ"
"Enjoy Your Life" by Dr. Muhammad 'Adb Al-Rahaman Al' Arifi

ነሃሴ - 2006 አዲስ አበባ

**ጃርቶቹ**





ክረምቱ እስከዛሬ ታይቶ በማይታወቅ ሁኔታ እጅግ ከብዶ ነበር። ከዜሮ በታች የወረደው ቅዝቃዜ የበርካታ እንስሳትን ህይወት ቀጠፈ። ብርዱን መቋቋም የተሳናቸው እንስሳት ከፍተኛ ስጋት ውስጥ ወደቁ። ከእንስሳቱ መሃከል የተፈጠረውን አስቸጋሪ ሁኔታ የተረዱት ጃርቶች ግን ሙቀት ለመፍጠር መሰባሰብ እንዳለባቸው ገመቱና በዚህ መንገድ እርስ በእርስ ተጠጋግተው በመቆማቸው ብርዱን መመከት ቻሉ። ይሁን እንጂ  እንደሚታወቀው ጃርቶች ሰውነታቸው በእሾህ የተሸፈነ በመሆኑ ይህ ጠላትን ለመከላከል የሚያግዛቸው እሾህ በተጠጋጉ ጊዜ እየወጋጋ አስቸገራቸው።

ከጥቂት ቆይታ በኋላ ስብስቡን አፍርሰው አንዳቸው ከአንዳቸው በመራራቅ እንደቆሙ ብርዱ ዳግም ያንዘፈዝፋቸው ጀመር፤ ከፍተት ያገኘው ቅዝቃዜ ተራ በተራ እንደበረዶ እያደረቀ ይገድላቸው ገባ። ቀስ በቀስ ለየብቻ በቆሙበት ሞት እየቀጠፈ ሲጥላቸው ሁለት ወሳኝ አማራጮች ከፊት ለፊታቸው ተደቀኑ። በመጠጋጋት የሚገጥማቸውን ጉዳት መቻልና አምኖ መቀበል ወይም አይናቸው እያየ አንድ በአንድ ከምድር ገጽ መጥፋት።

አርቆ በማስተዋል ጥበብ መክረው እንደገና ለመሰባሰብ በመስማማታቸው ገዳዩን ቁር ተቃቅፈው ተጋፈጡት። በህብረታቸው ውስጥ ከሚከሰትና አብሮነታቸው ከሚፈጥረው ቀላል ቁስል ጋር ተቻችሎ መኖርን ተማሩበት። በየመሃከላቸው ብርድ የሚያሳልፍ ክፍተት ሳይኖር እርስ በእርስ ተቃቅፈው፣ ሙቀት ተጋርተው ክፉ ቀን መሻገርን አወቁበት። በመጨረሻም የገዛ ገላቸው አካል ሆኖ በመጠጋጋታቸው ምክንያት እርስ በእርስ እየወጋ ካስቸገራቸው እሾህና ካስከተለባቸው ቀላል ህመም ጋር አብሮ መኖርን ተላመዱ። የትእግስትን በጎ መዳረሻ፣ በመቻቻል የሚገኝን አርኪ ውጤት መቋደስ በመቻላቸው ተርፈው መጪዋን የፀደይ ፀሃይ ለማየት በቁ ይባላል።

የሰው ልጆች ሁላችንም የየራሳችን የሆኑ ጠንካራና ደካማ ጎኖች አሉብን። ስንቀራረብና ስንጠጋጋ እየወጋጋ ያስቸግረናል፣ የአንዳችን ሃሳብ አንዳችንን ይጎረብጠናል፣ በአመለካከት፣ በአካሄድ፣ በትልምና መሰል ሁኔታዎች ብንለያይም የጋራችን በሆነ አንድ ራእይ ላይ መስማማት ይጎድለናል። ከሚያቀራርበን ይልቅ በሚያራርቀን ጉዳይ ላይ ስናተኩር በልዩነት ውስጥ ያለው የጋራ ጥቅምና አንድነት ይጋረድብናል። የተዋጣለት ህብረት ወይም እጅግ ምርጥ አንድነት ማለት የተመሳሳይ ግለሰቦች ስብስብ አይደለም፤ የጥሩ ሰዎች ጥምረት ማለትም አይደለም። እንከን የለሽ አንድነት የተለያየ ብቃት፣ ችሎታም ሆነ ድክመት ያላቸው ሰዎችን ያካተተ ሲሆን ነው። አንዱ የሌላውን ጉድለት የሚሞላ፣ ስህተቱን የሚያርቅና በጎ ጥረቱን የሚያደንቅ ሆኖ እያንዳንዳቸው በመተማመንና መቻቻል የፀኑ አባላትን የያዘ ህብረት እውነተኛው የአንድነት ምሳሌ ነው ማለት ይቻላል።

ወዳጆቼ! ስለመቻቻል ሳስብ የእኛንና የጃርቶቹን የትእግስት አቅም አወዳደርኩ፤ የሃሳብ፣ የአመለካከት፣ የአተረጓጎም፣ የአካሄድና መሰል ልዩነቶችን እንደመርፌ ከሾለ እሾህ ጋር . . . እናም ተቻችሎ መኖርን ለጠቆሙኝ ጃርቶች ጥቂት ስንኝ እንድቋጥርላቸው አነሳሳኝ። ለኛም ይሆነናል።

***<u>“መቻቻል”</u>***

*በገላችሁ ዙርያ - ሞልቶ ተደርድሮ*
*ጠላትን ሊመክት - ቆሞ ተወድሮ*
*እንደ ጦር የሾለው - የገዛ አካላችሁ*
*እንዳትጠጋጉ - መርገምት ሆኖባችሁ*

*ወጋግቶ ሸንቁሮ - አድምቶ መዝምዞ*
*ህመሙን አብዝቶ - ቆርቁሮ ገዝግዞ*
*አሰናካይ ሆኖ - አብሯችሁ ተፈጥሮ*
*አይጣል ተቆርጦ - አይርቅ ተወርውሮ*

*ችሎ መኖር እንጂ - ውጤቱን መዝኖ*
*አውቆት እንደናንተ - የሩቁን ወጥኖ*

*በሰከነ መንፈስ - መክሮ ተረጋግቶ*
*በፍቅር ተስማምቶ - በአንድነት ፀንቶ*

እኛን የገደደን - የራቀብን ከቶ
መዝለቅ እንደናንተ - መወሰን ሰንብቶ

ይህን ብሩክ መላ - እንዴት አወቃችሁ
ይህን የዘመን ፈውስ - እንዴት ተረዳችሁ
መወደስ ለናንተ - ምስጋናም ይግባችሁ
ጥላቻን በማረቅ - ከኛም ተሻላችሁ

የመቻቻልን ቅርስ - ያብሮነትን ውጤት
ተማርነው ከናንተ - የፍቅርን በረከት
ቁሩን ለመቋቋም - ብርዱን ለመመከት
ውርጨን ለማሸነፍ - ህይወት ለማሰንበት
ትንፋሽ ለመዋዋስ - ሙቀት ለመጋራት
ንፋስ እንዳይገባን - ክፍተቱን ለመዝጋት ።

ጠጋ በል ጠጋ በይ - ቅረቢኝ ቅረበኝ
አንተም ከንዴን እንካ - አንቺም እጄን ያዢኝ
እቀፊኝ ልቀፍህ - ልባችን ይቆራኝ
ከኛ ሌላ መድህን - ከቴውም ላይገኝ
ገፍተን ሰብሰብ እንበል - ቆርጠን እንገናኝ ።

ድርጊቴንም ባትወድ - ስሜትህ ባይጥመኝ
በሥራህ ብረበሽ - ጎኔን ቢያሳምመኝ
አመልህን ላርቅ - ፀባዬን ቻልልኝ
ህመምህን ላክም - ቁስሌን አብስልኝ
ድክመትህን ላርም - ጉድለቴን ሙላልኝ ።

ልዩነታችን እንዳለ - አምነን ተቀብለነው
በስብጥሩ ኮርተን - አምረን ተሸልመነው
በህብረታችን እንጽና - ፍቅራችንን እናልመው
ላንድነታችን እንቁም - ላብሮነታችን እናውለው ።

ይኼ ነው - መቻቻል - የማይነትብ ህብረት
ይኼ ነው - ቁንጅና - ጉራማይሌ ውበት
ይኼ ነው - መሰልጠን - ቂም አልባ አንድነት

ወረት የማይጎበኘው - በጎጠኝነት ያልታመመ
በመቻቻል ድር አብሮ - ሳይውተረተር የቆመ
ለዝንተ አለም የሚፀና - በሃቅ ማህተም የታተመ
ይኼ ነው - አንድነት - ይኼ ነው - ይኼ ነው - ይኼው ነው . . . ።

ምንጭ፡- የሥነ ምግባርና ቀስቃሽ ጽሁፎች ድረ ገጽ “ጃርቶቹ”
(Roger Darlington's World) "The hedgehogs"
የካቲት - 2008 *** አዲስ አበባ

## “ሀሴት . . . እና ~ የዘይቱ ጠብታዎች”

በድሮ ጊዜ ነው አሉ አንድ ሀብታም ነጋዴ ልጁ የደስታን ምስጢር እንዲማር በዓለም ላይ እጅግ አዋቂ ወደተባለ ሊቅ ዘንድ ላከው። ልጁ ወደ ሊቁ ቤት በሚያደርገው ጉዞ ለአርባ ቀናት ያህል አስገራሚውን የበረሃ መንገድ አቋርጦ ተራራው አናት ላይ

ወደተቆረቆረው የሚያምር ቅጥር ግቢ ደረሰ። ጠጋ ብሎ ሲያስተውል እንደገመተው ሥፍራው ፀጥ ረጭ ያለ በቅድስና ከሚኖር ትልቅ ሰው መኖርያነት ይልቅ ልዩ ልዩ የንግድ እንቅስቃሴዎች የሚከናወኑበት የደራ የንብ ቀፎ ይመስላል። በርካታ ነጋዴዎች ገባ - ወጣ ይላሉ። ወደ ውስጥ ሲዘልቅ ሰዎች በየጥጉ ሰብሰብ - ሰብሰብ ብለው ይነጋገራሉ። አንድ መለስተኛ የሙዚቃ ቡድን በመሳርያ የተቀነባበረ ለስላሳ ሙዚቃ ያንቆረቁራል፣ መሃል ለመሃል በረጅሙ የተዘረጋው ጠረጴዛ ላይ ግሩም ጣእም ያላቸው የተመረጡ የምግብ አይነቶች ተደርድረዋል።

ጠቢቡ ሰው በየቦታው ካሉ ሰዎች ጋር ያለመታከት በመነጋገር ተጠምዷል። ልጁ ይህንን ትእይንት እያስተዋለ ትኩረት እስኪያገኝ ለሰአታት መጠበቅ ነበረበት። በመጨረሻም ተራው ደረሰና አገኘው።

ሊቁ ሰው - ልጁ ለምን እንደመጣ የሚያደርግለትን ማብራሪያ በጥሞና ካዳመጠ በኋላ "አሁን የደስታን ምስጢር በሚገባ ልገልጽልህ አልችልም፤ ምክንያቱም እንደምታየው በጣም ጥድፊያ ላይ ነኝ። ይሁን እንጂ እስከዛው ድረስ ለሁለት ሰአት ያህል አስደናቂውን ዙርያ ግቢ ጎብኝተህ ብትመለስ ጥሩ ነው" የሚል ሃሳብ አቀረበለት። ወዲያውም አያይዞ "አንድ ጥያቄ ላቀርብልህ እወዳለሁ? በጉብኝትህ ወቅት ይህንን የሻይ ማንኪያ ይዘህ እንድትዘዋወር እፈልጋለሁ። ልብ በል! ላዩ ላይ ያለው ዘይት በምንም ዓይነት መፍሰስ እንደሌለበት ማወቅ አለብህ" በማለት ማንኪያውን ሰጠውና ላዩ ላይ ሁለት ጠብታ ዘይት ጠብ – ጠብ አደረገበት።

ልጁ በርካታ ደረጃዎችን እየወጣና እየወረደ፣ በኮሪደሮችና ሰፋፊ ክፍሎች ውስጥ እያለፈ ዐይኑን ከማንኪያው ላይ ሳይነቅል በዝግታ ግቢው ውስጥ ሲዘዋወር ቆይቶ ጠቢቡ ሰው ወዳለበት ቦታ ተመለሰ።

"መጣህ? በጣም ጥሩ። እንዴት ነው? በምግብ ቤቴ ግድግዳዎች ላይ የተሰቀሉትን ወደር የለሽ የፋርስ ስጋጃዎች አየህ? እውቁ የአትክልት ባለሞያ ለማጠናቀቅ አሥር ዓመታት የፈጀበትን እጹብ የተሰኘ የአበባ መስክስ ተመለከትከ? በመጽሃፍት ቤቴ የተሞሉትን እጅግ ድንቅ ስብስቦችስ አስተውለሃል?" በማለት አከታትሎ ጠየቀው።

ልጁ ደነገጠ፤ በእፍረት አንገቱን እንዳቀረቀረ ያስብ ጀመር። አዎ! የእርሱ ትኩረት በሙሉ በተሰጠው ማንኪያ ላይ ነበርና ዘይቱ እንዳይፈስ ሲጠባበቅ ምንም ያህል አላየም።

"በል ተመልሰህ ሂድና የኔን ግሩም ድንቅ አለም አስስ"። አለውና አያይዞ "አንድ ጥቅስ ልንገርህ - ቤቱን በሚገባ ካላስተዋልክለት ሰውየውን ለማመን አይቻልህም ይባላል" አለው።

ልጁም በእፎይታ ማንኪያውን አንስቶ ውቡን ግቢ ተዘዋውሮ ለመጎብኘት ወጣ። በዚህ ጊዜ ብዙ ነገሮችን ያገናዝብ ጀመር። በልዩ ንድፍ የተገነባው የህንፃው ውጫዊ አካል፣ የውስጥ ለውስጥ ጣርያና ግድግዳዎች ላይ ያረፉ የጥበብ ሥራዎችና ትንፋሽ የሚሰርቀው የአበቦች መስክ አፈዘዙት። የሥእሎቹና የመጽሃፍቶቹ ስብስብ ለመገመት የሚያስቸግር አድናቆት አሳደረበት፣ ቅጥር ግቢውን የከበበው የተራራ ሰንሰለትና አሉ የተባሉ ውብ ነገሮች ተሰባስበው የከተሙበትን ወደር የለሽ ሥፍራ አስሶ እንደተመለሰ ያየውን ሁሉ አንድ ባንድ ዘርዝሮ ለሊቁ ሰው አስረዳ። ሊቁም "ግሩም ነው! አሁን በደንብ አስተውለሃል። የዘይቱ ጠብታዎችስ የታሉ?" ሲል ቁልቁል ወደ ማንኪያው እየተመለከተ ጠየቀው። ልጁም ጎንበስ ብሎ ማንኪያውን አስተዋለ . . . ዘይቱ የለም፣ ፈሷል።

ከዚያም "ልጄ - ልለግስህ የምችላት አንዲት ትንሽ ምክር ብቻ አለችኝ" አለው የሊቆች ሊቅ - ሊቀ ሊቃውንት የሆነው ሰው እናም አያይዞ ቀጠለ . . . "የደስተኝነት ቁልፍ ምስጢር ማለት ግሩም ድንቅ የሆነውን አለም ማየት እናም በምንም አይነት ማንኪያው ላይ ያሉትን የዘይት ጠብታዎች ሳይዘነጉ እንደነበሩ መያዝ ነው"። በማለት ተሰናብቶት ሸኘው።

ይለናል እውቁ ብራዚልያዊ ፣ ገጣሚና ደራሲ ፐውል ሲልሆ "ዘ አልከሚስት" በተባለው መጽሃፉ ካቀረባቸው በርካታ መሳጭ ታሪኮች ውስጥ ክፍል አንድ ገጽ 17 ላይ እንዳሰፈረው ።

ሊቁ ሰው - ለልጁ የለገሰውን ምክር እኛም ልባችንን ከፍተን፣ ጆሯችንን ኮርኩረን በጥሞና ልናደምጠው የሚገባ ጥልቅ መልእክትና ሰፊ ትርጉም የሚቸረው ምሳሌ በመሆኑ እስቲ እንደዚህ እንየው። ደስታ – ማለት ምንድን ነው?። ከሳቴ ብርሃን ተሰማ የአማርኛ መዝገበ ቃላት የደስታን ትርጉም "የልቦና መደሰት፣ ሃዘን በሌለው ስሜት፣ ወለልታና የፊት ፍካት ደስ የሚያሰኝ ተድላን ማግኘት ነው" በማለት ያብራራል። እንደ ዊኪፔድያ (Wikipedia, the free encyclopedia) ደግሞ "Happiness is a mental or emotional state of well-being defined by positive or pleasant emotions ranging from contentment to intense joy. Philosophers and religious thinkers often define happiness in terms of living a good life, or flourishing, rather than simply as an emotion." ይለናል ባጭሩ።

ደስታ ፦ ጥሩ ኑሮን መምራት ሆኖ በእለት ተለት ህይወት ውስጥ የደህንነት ስሜትን የሚያድል፣ አስደሳችና ጠቃሚ በረከቶችን እንደሚሞላ አድርገን የምናስበው ሲሆን በሳቅ በፈገግታና ስኬትን በመሳሰሉ መልካም መገለጫዎች ታጅቦ እርካታን ለመንፈስ የሚመግብ እንደ ግለሰቦች ፍላጎት የተለያየና እንደየባህሪያቸው የሚወሰን የአእምሮና የጥልቅ ስሜት ውጤት ነው ማለት እንችላለን።

ቢሊዮኖች የተጠለልንባት ምድር የአምላክ ፈጠራና የሰው ልጆች ግኝት በሆኑ ሁለት አበይት ውጤቶች የተሞላች ናት። ከነዋሪዎቿ ውስጥ ጎሊናን የታደልንና ሰው በሚል መጠርያ የምንጠቃለለው፤ እኛ – ችግር፣ መከራና መሰል ጉዳቶችን የመሸሻችንን ያህል ፍስሃና ምቾትን ለሚያቋድሱ ነገሮች ያለን ቦታ ከፍተኛ ነው። ለዘመናት የኑሮን ፈተና በመጋፈጥ ሂደት ውስጥ የገጠሙንን መሰናክሎች ለመሻገር የከፈልናቸው የትንቅንቅ ውጤቶች የፈጠራ አድማሳችንን እያሳደጉት ሄደው እያደር እያንዳንዳችን በተለያየ ደረጃ ለምንሻቸው የደስታ መደላድል አይነቶች አቀብለውናል። እንደየ አቅማችን ደስታን እንሻለን፣ በኑሯችን ውስጥ ደስታን ለመቀዳጀት እንጥራለን። ደስታ ደግሞ አለማዊ ነው፣ የሰው ልጆች አእምሮና እጅ ሥራ ግኝት፣ የፈጠራ ውጤትና አበርክቶ ነው። የአለምን ድንቅ

ጥበብ ማስተዋል፣ ዙሪያዋን መቃኘትና መረዳት፣ በማራኪ፣ በአዝናኝና አማላይ ውበትዋ መደሰት የደስታ ምስጢር አንደኛው ጎን እንደሆነ ታሪኩ አሳይቶናል። ዋናውና የደስታ ምስጢርን ምሉእ የሚያደርገውስ ምንድን ነው ?።

ለዚህ ነው ሊቁ ሰው በማጠቃለያ ምክሩ "የደስተኝነት ቁልፍ ምስጢር ማለት ግሩም ድንቅ የሆነውን አለም ማየት እናም በምንም አይነት ማንኪያው ላይ ያሉትን የዘይት ጠብታዎች ሳይዘነጉ እንደነበሩ መያዝ ነው" በማለት የደስታን ምስጢር ለመማር አገር አቋርጦ ለመጣው ልጅ የገለፀው። ይህ እጅግ ጥልቅ የሆነ አባባል ከምንገምተው በላይ ትርጉም፣ ሰፋፊ ምሳሌዎችን ሊያጣቅስ የሚችልና እንደየ ብሄታችን የምንፈታው አገላለጽ መሆኑ እንዳለ ሆኖ ደራሲው "ግሩም ድንቅ ስለሆነው ዓለም" ባስቀመጣቸው ጥቂት ነጥቦችና ገሃድ ምልከታ አንፃር የደስታ ምስጢርን ግልጽ ጎን ማየት ችለናል።

✱ <u>"ማንኪያውና የዘይቱ ጠብታዎች"?</u> . . . ያላስተዋልነው "የደስተኝነት ቁልፍ ምስጢር" ምንድን ነው?።

ህይወት የሰጠንን፣ ጥበቃና በረከቱ ያልተለየንን፣ ይህንን ጊዜና ደስታ የለገሰንን ፈጣሪ አለመዘንጋት። ቃሉን በመጠበቅና ትእዛዙን በማክበር ዘወትር በምስጋና ውስጥ መራመድን መቻል። በአለም አለማዊ ደን ውስጥ ጠልቀን በሰው ሰራሽ ውብ ውጤቶቿ ተማርከን፣ ከእምነታችን እንዳናፈነግጥና የተሰጠንን የአምላክ አደራ እንዳንረሳ ለማስገንዘብ ነው። ስልጣኔን ስናወድስ፣ ጥበብና ተፈጥሮን ስናደንቅ ሁሉንም ነገር የለገሰንን አምላክ እንዳንረሳና ሟቹ ምድራዊ አካል እስትንፋሳችን ዘላለማዊ ህይወታችንን እንዳያሸንፍ መጠንቀቅ እንዳለብን ለማመላከት ነው። አእምሯችን ተዘናግቶ የጨበጥነውን በረከት እንዳንንቅ፣ አካላችን ዝሎ የያዝነውን የምህረት ዘንግ እንዳንጥልና ቃሉን በከንቱ እንዳናፈስ ለማሳየት ነው።

እንግዲህ ሌላውና አንጋፋው የደስተኝነት ገጽ የአምላክ ጽኑ እምነት ነው። ፍቅርን የተመላ ሰማያዊ ህይወትና ዳር የሌለው የቸሩ ፈጣሪ መንገድ ነው። በአጠቃላይ እውነትና . . . እውነት ማለት ነው። በእውነት ውስጥ ደግሞ ብዙ ሰብአዊ ተግባራት አሉ። ስንጠግብና ስንረካ – የተራቡና የተጠሙትን ማስታወስ፣ ስንለብስና ስንደርብ – የታረዙና የተራቆቱትን ማሰብ፣ ስንደሰትና ስንፈነጭ – በሃዘንና በመከራ ውስጥ ያሉትን አለመዘንጋትና ወዘተ . . . የመሳሰሉ በድርጊት የሚገለጹ መሰረታዊ ነጥቦች ናቸው።

ምድራዊ ደስታን ካሻንና ትክክለኛ ምስጢሩን መረዳት ከፈለግን ሁለት ሆነው በአንድ ማእቀፍ ውስጥ የተቀመጡትን ጥንድ ጽንፎች በተመሳሳይ ወቅት ማራመድ ግድ ይለናል። ትኩረታችን በሙሉ አንድ ነገር ላይ ሆኖ ደመ ነብሳችንን የተፈጥሮን ውበት ሳናደንቅ፣ የሰው ልጆች በተቸራቸው እውቀት ያፈሩትን ልብ ሰራቂና ማራኪ የጥበብ ውጤች ሳናስተውል የቱንም ያህል ስንዳክር ብንውል ልፋታችን – እንደ ልጁ አንድ ይጎድለዋል።

እነዚህን መንፈሳዊና ስጋዊ አጀንዳዎች በሚዛን ከዳኘን፣ እነኝህን ሁለትዮሽ ተግባራት በብቃት ከከወንን ብቻ በዓለም ቆይታችን የመደሰትን ምሉእ ምስጢር ተረዳን፣ ምድራዊውን የደስታ በር የምንከፍትበት ትክክለኛ ቁልፍ እጃችን ገባ ማለት ይቻላል። አሊያ አበው እንዳሉት "አንዱን ጥሎ አንጠልጥሎ" ይሆንብናል ማለት ነው። የመጽሃፉ ደራሲ "ፓውል ሲልሆ ስለ "ማንኪያውና የዘይቱ ጠብታዎች" ተምሳሌታዊ አባባል ያስቀመጠውን ማብራሪያም ሆነ ትርጉም ለማየት አልቻልኩም። ክፍተቱን ተጠቅሜ እንደ እኔ ግን ከላይ ያልኩትን ብያለሁ።

የተከበራችሁ አንባብያን ሆይ ! እናንተም እንደመሰላችሁና እንደየአመለካከት አድማሳችሁ በየትኛውም ጎን የመፍታት፣ በተቃራኒም ይሁን ተመሳሳይ አቅጣጫ የመተርጎምም ሆነ የመረዳት ሙብታችሁ ከእኔ በተሻለ ሁኔታ የተጠበቀ ስለመሆኑ ቃሌን ሰጠሁ። እስቲ ተመራመሩበት . . . ምን ይለናል - ቢያንስ እንማርበታለን።

ደራሲ ፡ ፓውል ሲልሆ (Paul Coelho)
ምንጭ ፡ የመጽሃፉ ርዕስ ፦ "ዘ አልከሚስት" ("The Alchemist")
መጋቢት - 2008 ✱ አዲስ አበባ

## <u>ጥቁሩ ነጥብ</u>



ከእለታት በአንዱ ቀን ፕሮፌሰሩ ከተለመደው አረማመዱ ፈጠን ፈጠን እያለ ወደ ክፍሉ ገባ። በሩ አጠገብና በአካባቢው የነበሩት ወጣቶችም ተከተሉት። ሁሉም መግባታቸውን እንዳረጋገጠ . . . "ተማሪዎች ዛሬ በድንገት ከዋናው ፈተና ጋር የሚያዝ አንድ ሙከራ እሰጣችኋለሁ" አላቸው። ተማሪዎቹም በያሉበት እንደተቀመጡ በፀጥታ ይጠባበቁ ጀመር። ከመጀመርያው ረድፍ በመነሳት እስከመጨረሻው ድረስ በክፍሉ ውስጥ እየተዟዟረ ጽሁፉን ወደ ውስጥ በመድፋት የፈተናውን ወረቀት ከያንዳንዳቸው ፊት ለፊት አስቀመጠላቸው። ከዚያም ጥቂት ቆይቶ የእጅ ሰአቱን መልከት አደረገና እንዲጀምሩ ትእዛዝ አስተላለፈ። ሁሉም ወረቀቶቻቸውን ገለበጡ፤ ነገር ግን በግርምት እንዳፈጠጡ ቆዩ።

ምንም ጥያቄ ያልተፃፈበት ባዶ ወረቀት ሲሆን መሃከሉ ላይ አንድ ክብ ጥቁር ነጥብ ብቻ ሰፍሮበታል። ፕሮፌሰሩ ግራ ለተጋቡት ተማሪዎቹ ድምጹን ከፍ አድርጎ "ተማሪዎች ፈተናው የመጀመርያው ገጽ ላይ ያያችሁትን ሁለተኛው ገጽ ላይ በሚገባ ተንትናችሁ መግለጽ ብቻ ነው" በማለት ስለጥያቄው አብራራላቸው። እነሱም በታዘዙት መሰረት መስራታቸውን ቀጠሉ።

ሁሉም የተፈቀደላቸው ጊዜ ከመጠናቀቁ ጥቂት ደቂቃዎች ቀደም ብለው ጨረሱና አስረከቡት። ፕሮፈሰሩ የመልስ ወረቀቶቹን ሰበሰበና ከፊት ለፊታቸው ሆኖ ያነብላቸው ጀመር። ያለምንም ልዩነት ሁሉም ስለ ጥቁሩ ነጥብ በተለያየ መልክ ለመግለጽ ሞክረዋል። እጅግ የጠቆረ አንድ ድቡልቡል ነጥብ፣ ከግራና ከቀኝ እኩል ቦታ መሃከል ላይ የተቀመጠ ትንሽየ ጥቁር ኳስ፣ ትኩር ብለው ሲያዩት የሚጠብና የሚሰፋ ጨለማ የሚመስል ክብ ቅርጽ . . . ሌላም ሌላም ዘርዝረዋል። የሁሉም መልስ ተነቦ እንዳለቀ ክፍሉ በፀጥታ ተዋጠ፣ ፕሮፌሰሩም በዝግታ ተነስቶ ማብራራቱን ቀጠለ።

"ልጆቼ! የዚህን ፈተና ውጤት አልይዘውም፣ ነገር ግን አንድ ቁም ነገር እሰጣችኋለሁ እናም በጥልቀት እንድትመረምሩት እሻለሁ። እስቲ ሁላችሁም ስለሰጣችኋቸው መልሶች አስቡ?። አንድም ሰው ስለ ወረቀቱ ነጭ ክፍል የፃፈ የለም፣ የእያንዳንዳችሁ ትኩረት በጥቁሩ ነጥብ ላይ ብቻ ነበር። ሰፊው የወረቀቱ ክፍል ነጭ ሆኖ ሳለ ሁላችሁንም የሳበው እጅግ በጣም ትንሹ ጥቁር ጠብታ ነው። ልብ በሉ ነገሮች በህይወታችን ውስጥ የሚከሰቱትም ልክ እንደዚህ ነው። የምነግራችሁ ርእስ በቀጥታም ይሁን በተዘዋዋሪ እስከ ህይወታችን ፍፃሜ አብሮን የሚኖር፣ ቀፍድዶ እንደያዘንና በተጽእኖው ስር እንዳሳደረን የሚቆይ እናም በጥንቃቄ ልናስብበት የሚገባ እጅግ ወሳኝ ጉዳይ ነው።

ሁላችንም እጅ ላይ ዘና የሚያደርገን ሰፊ ፀአዳ ገጽ (ነጭ ወረቀት) አለ፣ ይሁን እንጂ ትንሹ ሰንካላ (ጥቁር ነጥብ) ቀልባችንን ሰውሮት ስለእርሱ ብቻ በማብሰልሰል ተወጥረናል። ህይወት ታላቅ ስጦታ ነው፣ ዘወትር በሚያስደስት ድባብ እንድናከብረው በሚያደርጉ ሰበቦች የተሞላ እጅግ ድንቅ በረከት! . . . ምን ያደርጋል? በተሳሳተው ግንዛቤአችን የተነሳ ልናየው አቅቶናል፤ የሚታየን ጥቁሩ ነጥብ (ክፉ ክፉው) ብቻ ነው።

እያንዳንዱ ቀን ይቀያየራል፣ ይመጣል - ይሄዳል - ይለወጣል - ይታደሳል፤ፍቅራችን፣ ቤተሰቦቻችን፣ ጓደኞቻችን፣ ኑሯችን፣ ሥራችንና ሁሉም በየእለቱ ያለማሰለስ የሚከሰቱ ተአምራቶች፣ የሚጠበቁ ድርጊቶችና የሚናፈቁ ትእይንቶች ሁሉም እንዳናስተውል የተጋረዱብን ገሃድ ለውጦች . . . እንደ ወረቀቱ ነጭ ክፍል ትኩረት ነፍገን እንደተዳፈኑብን የቀሩ ነገሮች ናቸው። እናም እያደር አንለወጥም፣ ጥቁሩ ነጥብ ላይ ያለን ትኩረት ለአፍታም አይለዝብም፣ በጎውን ሳይሆን እኩዩን፣ መልካሙን ሳይሆን ተቃራኒውን ብቻ እናያለን። ይይዘናል ብለን ስለምንጠረጥረውና ስለምንፈራው በሽታ፣ እንዲኖረን ስለምንፈልገው ንብረት፣ ስለምንመኘው የገንዘብ ቁልል አልያም በጭራሽ ስለሌለንና አይተን ስለማናውቀው ቅንጦት ብቻ ሌት ተቀን እናስባለን። እጃችን ላይ ስላሉት ነገሮች ግን - ምንም።

ከሰዎች ጋር ባለን የእለት ተእለት ግንኙነት ደካማ ችግርና ሳንካ ስላለባቸው ነገሮች ብቻ፣ ስለተበሳጨንባቸው የቤተሰባችን አባላት፣ ስለተናደድንባቸው ጓደኞቻችንና ስለመበለጣችን እንጨነቃለን። ገና ለገና ስላቄምንባቸውና ስለምንጠላቸው ሰዎች ብቻ ትኩረት እንሰጣለን። ዘወትር ስለእነሱና ሥለ ግንኙነታችን፣ እንዴት እንደምንጥላቸው፣ በምን ዘዴ እንደምንልቃቸው ብቻ በማሰብ እንብከነከናለን። እስቲ ዞር ዞር ብለን እንይ፣ በእነዚህ ነገሮች ላይ የምናባክነውን ጊዜ እናስብ። ጥቁሩ ነጥብ በጣም ትንሽ ነው፣ አእምሯችንን የሚመርዘውም ይህ ኢምንት ነገር ነው። ክፉ ክፉው የህይወታችን ክንዋኔ፣ ስህተትና ስህተት የመሰሉን አጋጣሚዎች አልያም የሚያስጨንቁን ጥቂት ነገሮች . . . እንደ ሚጢጢው ጥቁር ነጥብ ሆነው ሳለ እኛ በራሳችን ትኩረት ሰጥተን ያገዘፍናቸው ጉዳዮች ተጽእኖ እንዲያሳድሩብንና እንዲቆጣጠሩን ከልክ በላይ የፈቀድንላቸው ይመስለኛል።

ዓይናችንን ከጥቁሩ ነጥብ ላይ እንንቀል፣ ከህይወት መንገዳችን ላይ ገለል አድርግነው የወረቀቱን ሰፊ ነጭ ክፍል እንመልከት። እያንዳንዳችን ስለተለገሰን የተባረከ ስጦታ እናስብ፣ ሥለ ሙሉ ጤናችን፣ በሰላም ወጥተን ስለመግባታችንና ተኝተን ስለ መንቃታችን ሁሉ እናመስግን። ስለተደሰትንባቸው ቀናት፣ ስለተማረክንባቸው ግኝቶች፣ ስለወደዱንና ስለወደድናቸው ደግ ደግ ሰዎች እናስታውስ። ስለፍቅር፣ ስለቤተሰብ፣ ስለ መልካም ሥራ፣ ስለ በጎ ምግባር . . . ወዘተ ብዙና ሰፋፊ ነገሮች እናስተውል። ለምን ስለትንሿ ጥቁር ነጥብ ብቻ በማሰብ ስንባዝን እንኖራለን?። ወዳጆቼ - በዚህ ድንቅ መርህ ህይወታችንን ምሉእ ደስታ እናላብሰው።

**ምንጭ ፡ www.All Time Short Stories.com**
**"The Black Dot"**
**ሃምሌ - 2008 (ዓ. ም.) * ላንጋኖ**



**"ቅን ህሊና"**

ዝግጅቱን አጠናቆ ከወደቡ ሊንቀሳቀስ የነበረው መርከብ ሞተሩ በድንገት ተበላሸ። የመርከቡ ባለቤቶች በርካታ ባለሞያዎችን እያቀያየሩ ሞከሩ። አንዳቸውም የብልሽቱን መንስኤ ሊያውቁና ሊጠግኑ አልቻሉም። በመጨረሻ ከወጣትነቱ ጀምሮ መርከቦችን ሲጠግን የኖረ አንድ ብርቱ ሰው ተገኘና ተጠራ። ሽማግሌው መሳርያዎቹን በትልቅ ቦርሳ ተሸክሞ መርከቡ ውስጥ እንደገባ ሞተሩን ከላይ እስከ ታች በመመርመር እክሉን ለማግኘት ይጥር ጀመር።

ሁለቱም የመርከቡ ባለቤቶች በቅርብ ሆነው ይሳካለት ይሆን? በሚል ተስፋ እያንዳንዱ እንቅስቃሴውን ይከታተሉ ነበር። ሽማግሌው ሰው ምርመራውን እንዳበቃ ከቦርሳው ውስጥ አንድ መዶሻ አውጥቶ የከፈተውን ሞተር የላይ አካል እየመረጠ መታ - መታ - አደረገ። በመጨረሻም የመርከቡ ሞተር ህይወት ዘርቶ ተነሳ። ሽማግሌው መዶሻውን ወደ ቦርሳው መለሰና ወጥቶ ሄደ።

ከዚያም ከአንድ ሳምንት በኋላ ሽማግሌው ለመርከቡ ባለቤቶች 20,000 ብር እንዲከፈለው የሂሳብ መጠያቅያ ሠነድ ላከላቸው። የመርከቡ ባለቤቶች ተገረሙ "ምንም የሠራው ከባድ ነገር ሳይኖር እንዴት ይህን ያህል ገንዘብ ይጠይቃል?" በማለት ተበሳጩበት። ወዲያው የተሠራውን ሥራ በዝርዝር የሚገልጽ የሂሳብ መጠየቅያ ሠነድ እንዲልክላቸው ደብዳቤ ፃፉለት።

ሽማግሌውም  የሚከተለውን ሠነድ ላከላቸው

**<u>የሂሳብ መጠየቅያ ሠነድ</u>**

| ተ.ቁ | ዝርዝር መግለጫ | ዋጋ ብር - ሣንቲም |
|---|---|---|
| 1. | በመዶሻ ለመምታት - - - - | 2.00ብር |
| 2. | የሚመታበትን ቦታ ለማወቅ | 19,998.00ብር |
| | **ጠቅላላ ድምር** | **20,000.00 ብር ብቻ** |

እናመሰግናለን!

ይላል ።

መጣር - መልካም ነው፣ መታገልና መድከምም እጅግ በጎ ናቸው። ነገር ግን ጥረትና ድካማችንን የት ቦታ ላይ ማዋል እንዳለብን ማወቅ ሁኔታዎችን ሁሉ የሚቀይር ቁንጮ የጥበብ ግኝት ነው። የመርከቡ ባለቤቶችም ያልተገነዘቡት፣ እኛም በየእለቱ ሳንረዳው የሚያልፈን ይኸው ሃቅ ነው።

የምንመዘነው በውጤቱ ሳይሆን - በፈጀው ጊዜና ጉልበት በመሆኑ እስከዛሬ የስንቱን ታታሪ የአእምሮ አገልግሎት መና እንዳስቀረንና የስንቱ ሠራተኛ ወዝና ላብ እንዳለፈብን ዞር ብለን ብናስተውል በውጤቱ የምናፍር ይመስለኛል ።

**ውጤት የሚያገናዝብ ቅን ህሊና ያድለን !!!**

ምንጭ: ዘ ጋርድያን -
Oliver Burkeman in "The Guardian Weekend", 13 August 2011
ግንቦት - 2006 * አዲስ አበባ



## <u>"ካሮት፣ እንቁላል እና ቡና"</u>

ልጅት ወደ እናቷ ቤት የሚወስደውን መንገድ ከሩጫ ባልተናነሰ ፍጥነት እያቆራረጠች ተጉዛ እቤት ስትደርስ በድካም ጥውልግልግ ብላ ነበር። ወደ ውስጥ ዘልቃ እናቷን ፊት ለፊት ስታገኛት የታመቀ ብሶቷ ፈነዳ - የእንባ ሳግ እየተናነቃት የህይወቷን

ምስቅልቅል ፈተና ትዘረዝር ጀመር . . . "እ ማ ማ ሁሉም ነገር ከብዶኛል፣ አንዱን ችግር ስጋፈጥ ሌላው መከራ ይደቀንብኛል፣ ምን ማድረግ እንዳለብኝ አላውቅም፣ መቋቋም ከምችለው ባላይ ሆኖብኛል። መላው በጠፋ የኑሮ ጨለማ ውስጥ ወድቄአለሁ" እያለች በምሬት ስታለቅስ ታሳዝን ነበር።

የልጇን ሁኔታ በጥሞና ስታስተውል የቆየችው እናት እጇን ያዝ አደረገችና ወደ ኩሽናቸው ወሰደቻት። ከዚያም ሦስት ድስቶች አውጥታ ውሃ ሞላቻቸውና ምድጃዎቹን ለኩሳ የእሳቱን ሃይል ከፍ በማድረግ ሦስቱንም ድስቶች ጣደች። የምታበስላቸውን ነገሮች እስኪታዘጋጅ ውሃው መፍላት ጀመረ። ወዲያው በመጀመርያው ድስት ውስጥ ታጥበው የተዘጋጁ ካሮቶች፣ በሁለተኛው ድስት ውስጥ እንቁላሎች፣ በሦስተኛው ውስጥ የተቆላ ቡና ጨመረች።

ከዚያም እስኪፍለቀለቁ ድረስ ጥዳቸው ልጇ አጠገብ ቁጭ ብላ ለሃያ ደቂቃዎች ያህል ጠበቀችና የምድጃዎቹን እሳት አጠፋች። እስከዚህ ድረስ ምንም ቃል አልተነፈሰችም ነበር። ጎድጓዳ ሳህን አቀረበችና በመጀመሪያ ካሮቶቹን ቀጥሎ እንቁላሎቹን ወደ ጎድጓዳ ሳህን አውጥታ በመጨረሻ ቡናውን ወደ ኩባያው ጨለፈች። ከዚያም ወደ ልጇ መለስ ብላ "እስቲ ምን እንዳየሽ ንገሪኝ?" በማለት ጠየቀቻት።

ልጅት - "የበሰለ ካሮት፣ የተቀቀለ እንቁላል እና የፈላ ቡና" በማለት መለሰችላት። እናትም ጠጋ ብላ ካሮቱን እንድትቀምሰው ጠየቀቻት። ቀመሰችና በደንብ በስሎ ለስላሳ መሆኑን ገለፀችላት። በመቀጠል እንቁላሉን እንድትሰብረው አዘዘቻትና ቅርፊቱን ፈልቅቃ የተቀቀለ ጠንካራ እንቁላል አወጣች። በመጨረሻ ቡናውን እንድትቀምስ ነገረቻት። ልጅቱም ቡናውን እንደቀመሰች በጣእሙ መርካቷን ፈገግ በማለት ገለፀች። አያይዛም "እማማ ይህ ሁሉ ምንን ያመለክታል?" በማለት እናቷን ጠየቀቻት።

እናትየውም ታብራራላት ጀመረች "እነዚህ ሁሉም ነገሮች ተመሳሳይ መከራን ተጋፍጠዋል - <u>የሚፍለቀለቅ ውሃ</u>። ይሁን እንጂ የእያንዳንዳቸው ምላሽ የተለያየ ሆኗል። ካሮት ሲጀመር ደረቅ፣ ጠንካራና የማይበገር የነበረውን ያህል በሚፍለቀለቅ ውሃ ሲፈተን ለስላሳና ደካማ ሆነ። እንቁላል ውስጣዊ ፈሳሹ በስስ ቅርፊት የተሸፈነና በቀላሉ ተሰባሪ ነበር። ነገር ግን የሚፈላ ውሃ ውስጥ መቀመጡ የውስጥ አካሉን ወደ ጠጣርነት ቀየረው። የተቆሉት የቡና ፍሬዎች ግን ልዩ ነው፣ በሚያስገርም ሁኔታ የሚፍለቀለቀው ውሃ ውስጥ በቆዩ መጠን የቀየሩት የሚያንተከትካቸውን ውሃ ነው"።

እናት የልጇን አይን ትኩር ብላ እያየች፤ "አንቺ የትኛውን ነሽ?" አለቻት። "መከራ ደጅሽን ሲያንኳኳ እንዴት አድርገሽ ነው የምትመልሽው?። ካሮት ነሽ? እንቁላል ነሽ? ወይስ የቡና ፍሬ?። እስቲ እኔ ማነኝ? ብለሽ አስቢ። እኔ ካሮት ነኝን? ሲያዩኝ ጠንካራ የምመስል ነገር ግን በመከራና ችግር ውስጥ ጉልበቱ ዝሎ በተስፋ መቁረጥ ጥንካሬዬን ሰውቼ ወደ ለስላሳነት የምቀየር። እኔ እንቁላል ነኝ እንዴ? ከመነሻው የነበረኝን ለስላሳ ልብ ሙቀት የሚቀይረው? ውስጤ በፈሳሽ ስሜት የተሞላ ነገር ግን በመከራና ስቃይ ውስጥ ሳልፍ በእሳት ፈተና ውጫዊ አካሌ ሲያዩት የነበረውን የሚመስል፣ ነገር ግን እኔነቴን ሽፍጩ የማስመስል፣ ውስጤ በስሜት አልባነት ደድሮ፣ ልቤ ወደ ጠጣርና የማይገባው ደረቅ ማንነት የሚቀየር። ወይስ የቡና ፍሬ ነኝ?። እውነቱን ለመናገር ራሴን ሳይሆን የፈላውን ውሃ ቀይሬ። በሚገርም አኳኋን በተፍለቀለቀ መጠን ጥልቅ ህመም የሚያስከትለው ውሃ ግሩም መአዛና ጣፋጭ ጣእም እንዲቀዳጅ የማድረግ ብቃት ያለኝ። እኔ የትኛው ነኝ? በይና ራስሽን መርምሪ።

አንቺ እንደ ቡና ፍሬ ከሆንሽ፤ ነገሮች ሲበላሹና ወደ ከፋ ደረጃ ሲያመሩ የተሻልሽ ሆነሽ በመገኘት በሚያስደንቅ ቅልጥፍና የአካባቢሽን ሁኔታ ትቀይሪያለሽ። የቀን ጨለማ ሲከብሽ፣ ችግር ጓዙን አብዝቶ ወደ ባሰ ፈተናና ስቃይ ሲሻገር፣ ጥንካሬና ትእግስትሽን አጎልብተሽ፣ የጠላትሽን መሰረታዊ ይዘት በዘዴ ቀይረሽ፣ በብቃት ለመፋለም ቆርጠሽ ትመክቻለሽ፤ እናም መከራን ተቋቁመሽ ታሸንፊያለሽ። ምርጫው ያንቺ ነው እንደ ካሮት፣ እንደ እንቁላል ወይስ እንደ ቡና?።

እስቲ እይው፣ አሽትችው፣ ቅመሽው፤ ውሃው በፈላና በተንተከተከ መጠን መአዛው እየናኘ እጅግ እየጣፈጠ ይሄዳል፤ ስለዚህ እንደ ቡናው ሁኚ። ከሚገጥምሽ ችግር ተማሪ፣ በመከራ ውስጥ አዲስ ነገር ቅሰሚ። ምንጊዜም ስኬትን አልመሽ ተነሺ። የምታደርጊውን ጠንቅቀሽ የምታውቂ ታጋሽና በጽናት እስከመጨረሻው የምትገፊ ቆራጥ በመሆን የሕይወትን ፈተና ተሻገሪ" በማለት እናት ልጇን ጠይቃ በመልሱ ውስጥ ልጂት ራሷን ፈልጋ እንድታገኝና እንድትማር አደረገቻት ይባላል።

እኛስ? የትኛውን ነን . . . ?

<u>**ካሮት? ወይ እንቁላል? ወይስ ቡና ፍሬ?**</u>

እስቲ ልጠይቅህ? ወዳጅ ወንድም ጓዴ
አንቺንም ልጠይቅ? እህቴ - ዘመዴ
የባህሪ ምስሉ አያያዝ ውሏችሁ
ተግባር ምስክሩ አስተሳሰባችሁ
የውስጣችሁ ብቃት ነብስያ ቀልባችሁ
ድካም ጥንካሬ ፈቃድ እምነታችሁ
ካሮት ወይ እንቁላል ወይስ ቡና ፍሬ
የቱን ይወክላል ? ልጠይቅ ደፍሬ

የመከራን ጊዜ የፈተናን ሰአት
የጨቀናን ዘመን የችግርን መአት

የስቃይን ገደል የምሬትን አዘቅት
የፍዳን አረንቋ የንግልትን ጅረት

በምን አለፋችሁ? እንዴት ተወጣችሁ?
እንደምን ቻላችሁ? ማን አሻገራችሁ?

እንደ ካሮት ጉማጅ ላሸቀ ገላችሁ?
እንደ እንቁላል አስኳል ጠጠረ ውስጣችሁ?
እንደ ቡና ፍሬ ገነነ ግርማችሁ?
ያ የቀን ጎደሎ ምን አስመሰላችሁ?

በምግባር መስታወት በተግባር መለኪያ
በልብ ላይ ሚዛን በድርጊት ማጣርያ
መዝኑት ለኩና . . .
ፈትሹት እዩና . . .
አቋም አሰላለፍ ጽናት ብቃታችሁ
የት እንደ ደረሰ - ውጤት ደረጃችሁ
ከማን እንደሚገጥም - ሥያሜ ልካችሁ
እንድትማሩበት ያዙት መዝግባችሁ።

ምንጭ፡- Roger Darlington's World
"The carrot, the egg, and the coffee bean"
ደራሲ፡ ያልታወቀ * ጥር - 2008 ዓ. ም. ~ ጅማ



**"ማሰብ ይቅደም"**




ታታሪው ሾፌር በሌሊት ተነስቶ ወደ ሥራ ቦታው አመራና ዘወትር እንደሚያደርገው የመኪናውን ደህንነት ፈትሾ ሞተሩን በማስነሳት፣ ግቢውን ለቆ ወጣ። የስምሪት አቅጣጫውን ይዞ አውቶብሱን እያሽከረከረ በተከታዮቹ የማቆምያ ጣብያዎች ጥቂት ሰዎች እየወረዱና አንዳንዶቹም እየተሳፈሩ፤ ሁኔታዎች በተለመደው አኳኋን እየሄዱ ነበር። አምስተኛው ማቆምያ (ፌርማታ) ላይ አንድ ረጅም ቁመናና ፈርጣማ ጡንቻዎች ያሉት የነፃ ትግል ተፋላሚ የመሰለ ግዙፍ ሰው ተሳፈረና ኋላ ካለው ወንበር ላይ እየተቀመጠ ድምጹን ከፍ አድርጎ "ትልቁ ጆን አይከፍልም" በማለት ተናገረ። ዞር ብሎ የተመለከተው ሾፌር በድርጊቱ እንደተከፋ ቢያስታውቅም ምንም ማለት አልቻለም። እኔ እንዳስተዋልኩት የከሲታው ሾፌር ዝምታ የተራራቀ የአካል ልዩነታቸውን መዝኖ ንዴቱን ስለመዋጡ፣ ፍም በመሰለው ፊቱ ያስታውቅ ነበር።

እኔ መቼም ከመነሻው ተሳፍሬ ለመጨረሻው ጣብያ አንድ ሲቀር የምወርድ የማለዳው አውቶብስ ደንበኛ ነኝ፤ በሚቀጥለው ጠዋትም ተመሳሳይ ድርጊት ተፈፀመ። ትልቁ ጆን ይሳፈርና እንደማይከፍል በማስታወቅ የሚፈልግበት ቦታ ሲደርስ ይወርዳል። በሦስተኛው፣ በአራተኛውና በቀጣዮቹ . . . ቀናትም ቀጠለ። ሾፌሩ መናቅና መበለጡ እያንገበገበው፣ ትልቁ ጆን ጉልበቱን ተማምኖ በደቃቃ ሰውነቱ ምክንያት እንደሚያጠቃው በማሰብ ቁጣና እልሁ እንቅልፍ እየነሳው መጣ። ብዙ አውጥቶና አውርዶ በመጨረሻ በአንድ ነገር ላይ ወሰነ። የአካል ብቃት እንቅስቃሴና የሰውነት ግንባታ ስፖርታዊ ስልጠናዎችን በመስጠት ከታወቀ ድርጅት ጋር ተዋውሎ በካራቴ፣ በጁዶ እንዲሁም በቀላል መሳርያዎች የመከላከልና ማጥቃት ልዩ ስልጠናዎችን መውሰድ ጀመረ።

ሌት ተቀን ጠንክሮ በመስራትና ያለውን ትርፍ ጊዜ ሁሉ ትምህርቱ ላይ በማዋል ከአመት ለበለጠ ጊዜ ተከታትሎ የከረምቱ መገባደጃ ላይ ስልጠናውን አጠናቀቀ። ከዚያማ የአካል ጥንካሬውና በራስ የመተማን ብቃቱ በከፍተኛ ደረጃ ማደጉ እየተሰማው እልሁን ለመወጣት አልመሽ አልነጋ ብሎት በጉጉት ሲብከነከን አደረ። ቀጣዩ ማለዳ ሰኞ ነበር። ሾፌሩ የወትሮ መስመሩን ይዞ አውቶብሱን ይነዳል፣ ትልቁ ጆን ተሳፈረና እንደለመደው "ትልቁ ጆን አይከፍልም" በማለት እልፍ ብሎ ተቀመጠ። ሾፌሩ ወዲያው መኪናውን አቆመና ወደ ኋላው ተፈናጥሮ በመዝለል በፍጥነት ተራምዶ ትልቁ ጆን አጠገብ ደረሰ። ቁልቁል እያፈጠጠበት . . . "ለምን? ስለምን አይከፍልም?" በማለት ጮኸበት።

ትልቁ ጆን በግርምት ተመለከተው። ቀኝ እጁን ወደ ሸሚዙ ግራ የደረት ኪስ ሰዶ ዙርያው አረንጓዴ ነጠብጣብ ያለበት መታወቅያ እያወጣ "ምክንያቱም ትልቁ ጆን ነፃ የአውቶብስ መጓጓዣ ፈቃድ ስላለው ነው" በማለት ከፍ አድርጎ አሳየው። ሾፌሩ ክው ብሎ መታወቅያ ካርዱ ላይ እንዳፈጠጠ አእምሮው በርካታ ነገሮችን ያሰላስል ጀመር። ምንም ማለት አልቻለም፣ ከቶ ምን የሚለው አለ?። እፍር ብሎ ወደ መሪው ተመለሰና ማሽከርከሩን ቀጠለ። እሱ ብቻ አይደለም እኔም አፈርኩለት። ከመጀመርያው ለምን ብሎ አለመጠየቅ፣ ጉዳዩን በቅን ኅሊና ከመመርመር ይልቅ በክፉና መጥፎ ጎኑ መጠርጠር፣ ገና ለገና በግዙፍነቱና በጉልበቱ ተመክቶ፣ በክሳቴ ንቆና ዝቅ አድርጎኝ ነው በማለት ለውሳኔ መቸኮል . . . የአውቶብሱን ሾፌር ምን እንዳስከፈለው አየን። የባከነው ገንዘቡ፣ እረፍት ያሳጣው የረጅም ጊዜ ስልጠና፣ ንዴት፣ ብስጭትና በቁጭት መብከንከኑ ሁሉ አላስፈላጊዎች ነበሩ።

እኛም በርቀት እየጠረጠርንና ባልተረጋገጠ እያመንን ለምን ያህል ውዝግቦች እንደምንዳረግ አስበን እናውቃለን?። በከንቱ ሳንባዝን፣ በተጨባጭ ሳንመዝን ከሚደርስብን የተለያየ የሥነ ልቦና፣ የአካልና መሰል ኪሳራዎች እንዳን። ብዙ ሳንሄድ አስቀድመን - ከመጋጨታችን በፊት ጠለቅ ብለን እናስብ . . . "ማሰብ ይቅደም"።

ምንጭ : ከ ማኅበራዊ ጉዳዮች ድረ ገጽ (useful thoughts. Collection)
"THINK BEFORE YOUR LEAP"
ሃምሌ - 2006 ዓ.ም. - አዲስ አበባ



## "የዝሆኖቹ ገመድ"

የተለያዩ የዱር እንስሳት የሚገኙበትን ታዋቂ ቦታ በመጎብኘት ላይ ነበርኩ። በግዙፎቹ ዝሆኖች አጠገብ ሳልፍ ግን ባየሁት ነገር እጅጉን ተገርሜ ቆምኩ። አንዱ እግራቸው በአንዲት ቀጪን ገመድ ብቻ ከመታሰሩ በስተቀር፤ ሰንሰለትም ሆነ አጥር የለም። ዝሆኖቹ በየትኛውም ሰዓት አካባቢውን ለቀው መሄድ ከፈለጉ ቀጭኗ ገመድ እንደማታግዳቸው ግልጽ ሆኖ እነሱ ግን ባልታወቀ ምክንያት ካሉበት አልተንቀሳቀሱም። ግራ ገብቶኝ ወዲያ ወዲህ ሳማትር አሰልጣኛቸውን አየሁትና ልጠይቀው ወደ እርሱ ተራመድኩ።

"ወዳጄ - እንዴት ነው እነዚህ ትልልቅ ዝሆኖች የትም የማይሄዱት? መቼም በዚህች ገመድ ታስረው ነው ማለት የማይመስል ነው" በማለት ጠየቅሁት።

አሰልጣኙም ፈገግ ብሎ "ገና በልጅነታቸው ትንንሾች ሳሉ የአሁኗን በምታክል ገመድ እናስራቸዋለን። በዚያን ወቅት በነበራቸው ጥንካሬ ቀጭኗ ገመድ ልታቆማቸው በቂ ነችና ታስረው ይቆማሉ። እያደጉ፣ እድሜአቸው እየጨመረና ሰውነታቸው እየፋፋ ቢመጣም አስተሳሰባቸው ግን አይቀየርም። እስካሁን እግራቸው ላይ የታሰረችው ቀጪን ገመድ የትም ከመሄድ እንደምታግዳቸው ስለሚያምኑ ዳግም ሞክረው አያውቁም። አንገላቸው መንቀሳቀስ እንደማይችሉ አስረግጦ እንደወሰነ ቀርቷል፤ እናም እንደምታየው ባናስራቸውም እንደታሰሩ ቆጥረው ቆመዋል"። አለኝና ትቶኝ ወደ ሥራው ሄደ።

እኔ ግን እነዚህ ከዓለማችን የየብስ ፍጡራን በትልቅነታቸው ቀዳሚውን ቦታ የያዙ እንስሳት፤ ተራራ በሚያክል ግዙፍ ሰውነታቸው ላይ በተቋጠረችና ለእነርሱ የክርን ያህል በምትገመት ቀጭን ገመድ መታገታቸው አስገረመኝ። ተስፋ ያስቆረጣቸው የሰበብ ቅንጣት ምስጢሩ ሊገለጽልኝ ባለመቻሉ፤ ለጥቂት ደቂቃዎች ቆሜ ሳስተውላቸው ቆየሁና ሌሎች እንስሳትን ለመጎብኘት የማእከሉን ግራ ጠርዝ ይዤ ጉዞየን ቀጠልኩ። አእምሮዬ ግን በዝሆኖቹ ውስጥ እኔን እየተመለከተ በተመሳሰሎና ተቃርኗችን ላይ መብሰልሰሉን አልተወም። እኛ የሰው ልጆች እንዲህ ካለው ጣጣ ጽዱ አለመሆናችንን ገሃዱ እውነት ያሳብቅብናል። በራሳችን ውስጥ በሚፈጠሩ ሁለት ተቃራኒ ሃሳቦች እንወጠራለን፣ ለመወሰን መቸገር በማቅማማት ረጅም ጊዜን ማባከንና ማንገራገር ሲፈትነን ከመቆየቱም በላይ ሳንመዝን ወደ ቀረበን ጎራ ማዘንበልና በኋላም በማናውቀው ተስማምተን ስናበቃ ከመሸ ወዲያ ሲገለጽልን መፀፀት የአብዛኞቻችን የጋራ ችግር ነው።

አጓጉል ባህል፣ ልማድና ረብ የለሽ ወግ . . . ከሽረሪት ድር በሳሳ ስንፍና ተብትቦን፣ ወሬ፣ በራስ አለመተማመንና ተስፈኝነት፣ ቀና ብለን ቀኑን እንዳናይ በፍርሃት ሸማ ጋርዶን፣ በነበርንበት ያለን ስንቶቻችን ነን?። ሳንሞክር ዳግም ላለመሞከር ተማምለን፣ ገና ለገና ራሳችን በፈጠርነው የማይታይ የምናብ ጭራቅ እየበረገግን፣ ከራሳችን ጋር እየተጋጨንና እየተጠላለፍን ያለ አሸናፊ ተሸንፈን የተዘረርን ስንት ነን?። የሚጥል በሌለበት በተስፋ መቁረጥ ብቻ እየወደቅን፣ ወይ አልጀመርን ወይ አልጨረስን በተንጋለልንበት እልፍ ጊዜ መሽቶ የነጋ ምን ያህል ነን . . . ?። ፩፣ ፪፣ ፫፣ ፬ . . . ምድሪቱ ትቁጠረን።

(ከ ሃያ አምስት ዓመት በፊት የፃፍኳት ግጥም ትዝ አለችኝና ፈልጌ አገኘኋት። እንዲህ ተደርድራ ነበር።)

"እኔና እኔነቴ"

እኔና - እኔነቴ
አካሌና - እምነቴ
ኑሮና - ፍጥረቴ
ጽድቅና - ሃጥያቴ

አንዱም ሳንታረቅ - ላንዱም ሳንስማማ
የሚለው ሳይገባኝ - ያልኩትን ሳይሰማ

ስራመድ - ሳቋርጥ
ስቆም - ስገላበጥ
ስነሳ - ሳዘግም
ስታቀብ - ሳገግም
ስነቃ - እየተኛሁ
ሳውቅ - እየተሞኘሁ

ሳሞግስ - ሳጥላላ
ስወደድ - ስጠላ
ስከፋ - እየጨፈርኩ
ሳገኝ - እያማረርኩ

ህልሜን - እያመለኩ
ቅዠቴን - እየኖርኩ

ሳልወድ - እያማረኝ
ሳልፈቅድ - እያሰኘኝ
ያጣሁትን - ስመኝ
የሌለውን - ሳገኝ
የያዝኩት - ሲያመልጠኝ
የሳትኩት - ሲቀርበኝ

አልራኩ - አልደረስኩኝ
አልተውኩ - አልጨበጥኩኝ

ምናብ እየበላሁ - ጉም እየዘገንኩኝ
እሮጣለሁ እንጂ - አሁንም እዚያው ነኝ

እኔና - እኔነቴ
አካሌና - እምነቴ
አንድ አይሉን - ሁለቶች
ባንድ ራስ - መአቶች

ስንከድ - ስናምን
ስናለቅስ - ስንዘፍን
ስንጠግብ - ሲርበን
ስንረካ - ሲጠማን
ስንፋፋ - ስንቀጥን
ስንልቅ - ስንመነምን
ስንቸር - ስንለምን
ደርበን - ሲበርደን
ታርዘን - ሲያምርብን

ነቅተን - እየተኛን
ቆመን - እየሄድን
በረን - እያረፍን
ደርሰን - እያለፍን
ለቀን - እያሳደድን
ሰብስበን - ስንበትን

ሮጠን አልቀደምን - ወይ ታክተን አልተውን
ቀርበን እየራቅን - አሁንም እዚያው ነን

እኔና - እኔነቴ
አካሌና - እምነቴ
አንድ ላይ ነን እንጂ - አንተዋወቅም
እሱንም አልመስል - እሱም አይመስለኝም

ሲያስጠጋኝ - ስገፋው
ሲረዳኝ - ስከደው
ሲቀማኝ - ስከፍለው
ሲያለብሰኝ - ስገፈው
ሲነክሰኝ - ሳጎርሰው
ሲያከብረኝ - ስንቀው
ሲጠላኝ - ስወደው
ሲመከረኝ - ስነቁረው

ላስመስል ? - ልቃወም
ልዳን ? - ወይ ልታመም

ዘምኜ - ልመንን
ጨምቼ - ልወምን

ማሽነፌን ላውጋ ? - መረታቴን ልመን ?
ከየቱ ልጠጋ ? - ከየቱ ልወግን ?

ልጋፈጥ . . . ? ልጠቃ ?
ሳልጀምር - ሳበቃ።

ብስራት ጴጥሮስ ዮሣ
ተፃፈ 1983 ዓ. ም. ጂማ

የታሪኩ ምንጭ፦ ማኅበራዊ ድረ ገጽ "The Elephant Rope" Power Point Presentation
መስከረም - 2007 ዓ. ም. * አዲስ አበባ




**አንድ ዶላር ከ አስራ አንድ ሣንቲም**

ቴስ ከእድሜዋ በላይ የምታስብ የስምንት ዓመት ብልህ ልጅ ነች። አንድ ከሰዓት አባትና እናቷ ስለ ወንድሟ አንድሪው የሚያወሩትን ሰማች። ከመላ ንግግራቸው የተረዳችው ነገር ወንድሟ በጠና ስለመታመሙና የሚያሳክሙበት ምንም ገንዘብ እንደሌላቸው ነበር። በብቸኛ አማራጭነት ለቀረው ውስብስብ ቀዶ ጥገና የሚፈለገው ከፍተኛ ገንዘብ መገኛው አጥሯል። እጃቸው ባዶ ነው፣ ብድር የሚያገኙበት መንገድም የለም። በቀጣዩ ወር አሁን የሚኖሩበትን ቆንጆ ቤት ለቀው ኪራዩ ረከስ ወዳለ ትንሽዬ ቤት ለመዛወር ቢወስኑም የሚተርፋቸው ገንዘብ እዚህ ግባ የሚባል አይደለም።

የሃዘን ድባብ ባረበበበት ጎጆ፣ የእንባ ሳግ የሚተናነቃት እናትና ተስፋ የቀረጠ አባት በሹክሹክታ ይወያያሉ። ቴስ – የአባቷን የሚርገበገብ ድምጽ ሰማች **"አሁን የልጄ ህይወት ሊተርፍ የሚችለው በተአምር ብቻ ነው"** እያለ እጆቹን አጣምሮ ከወዲያ ወዲህ ይንጎራደዳል።

ቴስ ሹልክ ብላ ወደ መኝታ ክፍሏ ሮጠች። ቁም ሳጥኑን ከፍታ ልብሶቹን በማንሳት ወደ አንድ ጎን እያደረገችና እጆቿዋን እየሰደደች ስትፈልግ ቆይታ አንድ ትንሽ የቅባት ጣሳ አወጣች። ከዚያም ቁጭ አለችና የቅባቱን ጣሳ በመክፈት ውስጧ የነበሩትን ሣንቲሞች ወለሉ ላይ ገልብጣ በጥንቃቄ መቁጠር ጀመረች። አንዴ – ሁለቴ . . . ለሦስተኛ ጊዜ ደግማ ቆጠረች ሁሉም ተመሳሳይና ትክክል ነው። አሁን ለስህተት ምንም አይነት እድል የሚሰጥበት ጊዜ አይደለም። ሳንቲሞቹን በዝግታ እየለቀመች ወደ ጣሳው መልሳ እንደነበረው በመክደን እቅፍ አድርጋ ያዘችው፤ ከዚያም ኮቴዋ እንዳይሰማ በቀስታ እየተራመደች በጓሮው በር በኩል ወጣች። በቀጥታ መንገዱን ተሻግራ ከስድስተኛው ህንፃ በስተቀኝ በኩል ወደሚገኘውና ትልቅ የቀይ ሕንዶች አለቃ ምስል ከተሰቀለበት ሬክሳል የመድሃኒት መደብር አመራች።

በሰፊው መደብር ባንኮኒውን ተንጠራርታ ወደ ውስጥ ስታስተውል ነጭ ካፖርት የለበሰው የመድሃኒት ቤቱ ሠራተኛ ጠረጴዛውን ተደግፎ፣ የሚያምር ሙሉ ሱፍ ለብሶ ቀላ ያለ ከረባት ካሰረ ሰው ጋር በተመስጦ ያወራል። ገብታ እስኪያየት ድረስ

በትዕግስት ጠበቀች . . . አላያትም። ወለሉን በጫማዋ አሸት አሸት አደረገች፣ አልሆነም። ጉሮሮዋን በመጠራረግ እ . . ህ - እ . . ህ አሳለች – ቀናም አላለ። ከጣሳዋ ጥቂት ሣንቲሞች አወጣችና መስታወቱን አንኳኳች፤ አሁን ቀና ብሎ አያትና ወደ እርሷ መጣ።

የመደብሩ ሰራተኛ በቁጣ አንደበት "ለረጅም ጊዜ ሳንተያይ ቆይተን ዛሬ ከቺካጎ ከመጣው ወንድሜ ጋር ብርቱ ጨዋታ ይዘን ነበር፤ ለመሆኑ ምንድን ነው የምትፈልጊው?" በማለት ጮክ ብሎ ጠየቃት።

ቴስ ተናደደች! ሰውየውን ወደ ላይ አፍጥጣ እያየች ከፍ ባለ ድምጽ "እሺ እኔ የምናገረው ስለ ወንድሜ ነው! ታሟል በጣም ታሟል፣ ተአምር ልገዛለት እፈልጋለሁ" አለችው።

ግራ በመጋባት "እባክሽ ደግመሽ ንገሪኝ?" አላት።

"ስሙ አንድሩ ይባላል። ጭንቅላቱ ውስጥ አንድ የማይታወቅ መጥፎ ነገር እየበቀለበት ነው፣ አባቴ ሲናገር እንደሰማሁት አሁን ህይወቱ ሊተርፍ የሚችለው በተአምር ብቻ ነው። እናም ተአምር ልገዛለት እፈልጋለሁ? የተአምር ዋጋው ስንት ነው?" አለችው።

"ትንሿ ልጅ እዚህ ተአምር አንሸጥም። ልረዳሽ ባለመቻሌ በጣም አዝናለሁ" በማለት ቀዝቀዝ ብሎ መለሰላት።

"ስማ? በደንብ አዳምጠኝ! የምገዛበት ገንዘብ አለኝ። ጥቂት እንኳን ቢጎለኝ ቀሪውን እፈልጋለሁ፣ ብቻ ዋጋውን ግለጽልኝ። ተአምር ስንት እንደሚሸጥ ንገረኝ!" አለችው የሳንቲም ጣሳዋን ከፍ አድርጋ በመነቅነቅ። የእንባ ጤዛ ያቋተው አይኗ ደፍርሷል፣ ትንሽየ ፊቷ ቀልታ የበሰለ ቲማቲም መስላለች። ያማረ ልብስ ለብሶ በርቀት ንግግራቸውን ያዳምጥ የነበረው የመደብሩ ሠራተኛ ወንድም በዝግታ ከወንበሩ ላይ ተነስቶ ወደፊት ቀረበና ጎንበስ ብሎ . . . "ወንድምሽ የሚያስፈልገው የትኛው ዓይነት ተአምር ነው?" በማለት ጠየቃት።

"በእርግጥ እኔ አላውቅም" ቴስ ዓይኗን አቁለጨለጨች። "ስለ እውነት እኔ የማውቀው በጣም – በጣም መታመሙን ነው። በተጨማሪ ማሚ ስትናገር እንደሰማሁት አስቸኳይ ቀዶ ጥገና ያስፈልገዋል፣ አባቢ ደግሞ ተአምር ያድነዋል ይላል፣ የሚከፍለው ምንም ገንዘብ የለውም። ለዚህ ነው የኔን ገንዘብ መጠቀም የፈለኩት" አለችው።

"እሺ ! ምን ያህል ገንዘብ አለሽ?" ጠየቃት ከቺካጎ የመጣው ሰው።

"አንድ ዶላር ከ አስራ አንድ ሣንቲም ነው፣ እናም ያለኝ ገንዘብ ይኸው ብቻ ቢሆንም ተጨማሪ ካስፈለገ ጥቂት የማገኝ ይመስለኛል" በማለት ዝቅ ብሎ በሚስረቀረቅ ድምጽ መለሰችለት።

"አ አ ው ይገርማል፣ በአጋጣሚ" ሰውየው ፈገግ አለ "በአጋጣሚ አንድ ዶላር ከ አስራ አንድ ሣንቲም – ለወንድምሽ የሚያስፈልገው ተአምር ትክክለኛ ዋጋ ነው!" አላት።

የቺካጎው ሰው ገጹ በብሩህ ፈገግታ እንደተመላ ጎንበስ ብሎ በአንድ እጁ የሣንቲም ጣሳዋን እየተቀበለ በሌላ እጁ ትከሻዋን ያዝ አድርጎ "እስቲ ወደ መኖሪያ ቤታችሁ ውሰጂኝ? ቤታችሁን ማየት፣ ከአባትና እናትሽ ጋር መወያየትና ስለምትፈልጊው የተአምር አይነት ማረጋገጥ እፈልጋለሁ" በማለት የደስታ ስሜት የሚነበብባትን ትንሽ ልጅ አበሰራት።

በሚያምር ሙሉ ሱፍ የተዋበው የቺካጎ ሰው፤ ታዋቂው የነርቭ ህክምና ስፔሻሊስትና የቀዶ ጥገና ሃኪም ዶክተር ካርልቶን አርምስትሮንግ ነበር። ወደ ቴስ ቤተሰቦች ቤት ሄዶ ከአባትና እናቷ ጋር በሰፊው ተነጋገረ። የአንድሪውና የአባቱን ሙሉ ወጪ ሸፍኖ ወደ ቺካጎ ወሰዳቸው፣ የቴስ ወንድም በተደረገለት የተሳካ ቀዶ ጥገናና በቸሩ አምላክ ፈቃድ ባጭር ጊዜ ተሽሎት ወደ ቤቱ ተመለሰ።

የቴስ አባትና እናት ካሳለፉት የፈተና ወቅት ጀምሮ በነፃ እስከተደረገላቸው የቀዶ ጥገና ድረስ፣ ለተቸራቸው ወደር የለሽ ውለታ በሚያቀርቡት ታላቅ ምስጋና ተጠምደው ሰነበቱ። በዚያው ሰሞን አንድ ምሽት ቤተሰቡ ሳሎን ውስጥ ተሰባስቧል። የቴስ አባት ከሥራ ተመልሶ ሶፋ ላይ ጋደም ያለው ልጁን ያጫውታል፣ የቴስ እናት ቴስን እያስጠናች የቤት ሥራዋን ስትሰራ በአንክሮ ታስተውላታለች። የሁሉም ዓይን ሰረቅ እያደረገ በሳቅ የሚፍነከነከውን ልጅ ያያል፣ ልቦቻቸውም እንደዛው። የቴስ እናት ድምጿን ከፍ አርጋ በአድናቆት "መቼም ለአንድሪው የተደረገለትን ቀዶ ጥገና ሳስብ ድንቅ ይለኛል! የሚገርም ተአምር ነበር። አቤት . . .? እንደው ስንት ገንዘብ ፈጅቶ ይሆን?" በማለት ባለቤቷን ጠየቀች።

ይህንን ስትሰማ ቴስ ፈገግ ብላ መፃፏ ላይ አቀረቀረች። ዋጋውን ምታውቀው እሷ ብቻ ናት። አንድ ዶላር ከ አስራ አንድ ሣንቲም . . . ሲደመር የትንሿ ልጅ ጽኑ ፍቅር ብቻ።

እውነትም ተአምር !።

እውነተኛ ታሪክ እንደሆነ በመጥቀስ (እአአ) በ 1999 ፊልም የተሰራበትና በተለየዩ ማኅበራዊ ድረ ገፆች ላይ የተሰራጨ ታሪክ። ፊልሙን መመልከት ለምትሹ "Miracle" by - Fred Bouchal Films
ሬክሳል የመድሃኒት መደብር፡ (እ.አ.አ) ከ 1910 ዓ.ም. ጀምሮ በበርካታ ሃገሮች በመድሃኒት አከፋፋይነት የታወቀ ኩባንያ ነው። (Rexall is a chain of American drugstores, and the name of their store-branded products. The stores, having roots in the federation of United Drug Stores starting in 1903)

ዶክተር ካርልቶን አርምስትሮንግ፡ አሜሪካዊ፣ ታዋቂ የነርቭ ህክምና ስፔሻሊስትና የቀዶ ጥገና ሃኪም ነበር። ምንጭ ፡ (Moral and Inspiration Stores Collection) "A Miracle of A dollar and eleven cents"

ሃምሌ - 2008 * አዲስ አበባ

**"ምስጋና"**



"አምላኬ ተመስገን" . . . "ጌታዬ ተመስገን" . . . ይህ ድምጽ አንዲት በኑሮ የተጎሳቆሉ አሮጊት ሴት በየእለቱ ጠዋት ጠዋት የቤታቸው በረንዳ ላይ ቆመው እጃቸውን ወደ ሰማይ በመዘርጋት የሚያሰሙት ቃል ነበር። እምነት የለሹ ጎረቤታቸው በዚህ የዘወትር ድርጊታቸው እጅግ ይበሳጭ ስለነበር እርሳቸው ምስጋናቸውን ሲያሰሙ እርሱም ይወጣና "አምላክ የሚባል ነገር የለም" . . . "ጌታም የለም" እያለ መሳለቁን ሥራዬ ብሎ ተያይዞታል።

በዚህ ዓይነት የቀጠለው የሁለቱ ጎረቤታሞች የየእለት ውዝግብ ለብዙ ጊዜ ቆየ። በክረምቱ አጋማሽ ውስጥ - አንድ ማለዳ የተለመደ ምስጋናቸውን ለማሰማት የወጡት አሮጊት "አምላኬ ተመስገን . . . ጌታዬ ተመስገን ርቦኛል! የምበላውን ስጠኝ? አቤቱ ፈጣሪ ሆይ ክበር - ተመስገን!" እያሉ ልመናና ምስጋናቸውን ሲያቀርቡ ጎረቤታቸውም “አንቺ አሮጊት የምን አምላክ፣ የቱ ፈጣሪ ነው? የሉም - የሉም” በማለት ሁሌም እንደሚያደርገው ጮክ ብሎ ተናገረና ወደ ቤቱ ገባ።

በሚቀጥለው ጠዋት አሮጊቷ ለምስጋና ሲወጡ በረንዳቸው ላይ በልዩ ልዩ ዓይነት ምግቦች የተሞሉ ሁለት ትልልቅ የፕላስቲክ ከረጢቶች (ፌስታሎች) ተቀምጠው አገኙ። "አምላኬ ተመስገን! የሻትኩትን አበርክተህልኛል፣ ልመናዬን ሰምተህ ሰተኸኛል! ተመስገን . . . ተመስገን" እያሉ ማመስገናቸውን ቀጠሉ። በዚህ ጊዜ እምነት የለሹ ጎረቤታቸው በንዴት ከቤቱ ዘሎ ወጣ። በቁጣ ድምጹን ከፍ አርጎ "አምላክ የለም! እነዚህን ምግቦች የገዛሁልሽ እኔ ነኝ! አምላክሽ አይደለም ያስቀመጥኩልሽ እኔ ነኝ! . . ." እያለ ይጮህ ጀመር።

ምስጋናቸውን ያላቋረጡት አሮጊት እጃቸውን ወደ ሰማይ እንደዘረጉ "አምላኬ ተመስገን . . . ሰይጣን እንዲከፍልባቸው አዘህ የለገስከኝ ምግቦች ደርሰውኛል! ጌታዬ ክበር ተመስገን! ተመስገን!" ቀጠሉ . . . የማለዳውን ቁር ሰንጥቆ በርቀት የሚያስተጋባው የአሮጊቷ ቃል ለእምነት የለሹ ጎረቤታቸው ብቻ የተሰነዘረ አልነበረም። እያየን ያሸለብነውን፣ እንቅልፍ የጣለንንም ሆነ አውቀን የተኛነውን ፍጡራን ሁሉ የሚያነቃ ነበር። አሮጊቷ የዘወትር ምስጋናቸውን አላስተጓጎሉም። ቢከፋቸውም - ቢደሰቱም፣ ቢርባቸውም

- ቢጠግቡም፣ ቢጎሳቆሉም - ቢደላቸውም . . . አላቋረጡም። ስንቶቻችን እንደሰማናቸውና እንደተማርንበት ግን የሚታወቅ ነገር የለም፣ ስንቶች እንደተከተሏቸውም እንጃ። እርሳቸው ግን፤ ዘወትር ያመሰግናሉ።

እኛስ ከምስጋና ምን ይጎልብናል? እስቲ ዞር ብለን የተደረጉልንን ቁጥር ስፍር የሌላቸው በረከቶች እናስተውል - የማናቸው? በማን ፈቃድ?። ለተሰጠን ካላመሰገንን ከነጠቃ አይቆጠርብንምን? መቼስ ነው የምናመሰግነው?። ወዳጆቼ ማመስገንን እንልመድ፣ አልያ ፋይዳ ቢሶች እንሆናለን። እምነት የለሹን ጎረቤት የመሳሰሉ በርካታ ግብዞች በራሳቸው እንዳደረጉ ያስባሉ፣ ማሰብ ብቻ አይደለም የነሱ ያልሆነውን መወደስ ይጠብቃሉ፣ ነገር ግን ከቶ ምንም አይደሉም "ትእዛዙ ከላይ ነው" ይባላል። ከላይ። በተለይ ሰጪዎች (ለጋሾች) ነን የምንልም የምንባልም፤ መስጠት ከእኛ አይደለምና በረከታችንን በዋዛ እንዳናረክስ እናስብበት።

ምንጭ ፡ ከሥነ ምግባር ትምህርቶች ድረ ገጽ www.moralconduct.com
"PRAISE THE LORD"

ሃምሌ - 2008 ዓ.ም. - አዲስ አበባ



**"ወጥመዱ"**



ራቅ ባለ አንድ የገጠር መንደር ውስጥ በግብርና ሥራ የሚተዳደሩ ባልና ሚስት ነበሩ። ከእለታት በአንዱ ቀን ከገበያ ተመልሰው የገዙትን እቃ ከዘንቢል ውስጥ እያወጡ ያስቀምጣሉ። ግድግዳው ስር ከትንሿ ጉድጓዱ ጥግ ሆኖ ወደ ውስጥ የሚመለከተው አይጥ የሚከፈተው ካርቶን ውስጥ ምን አይነት ምግብ ይኖር ይሆን? በሚል ጉጉት በተመስጦ ይከታተላል። ይሁን እንጂ ሰዎቹ አዲስ የአይጥ ወጥመድ መዘው ሲያወጡ አየና ከፉኛ ደነገጠ።

በድንጋጤ የበረገገው አይጥ ሸሽቶ በመሮጥ "ቤቱ ውስጥ የአይጥ ወጥመድ አለ!" - "ቤቱ ውስጥ የአይጥ ወጥመድ አለ!" በማለት ድምጹን ከፍ አድርጎ እየጮኸ ግቢው ውስጥ የሚገኙ እንስሳትን ሁሉ ማስጠንቀቅ ጀመረ። በመጀመሪያ ያገኘው ዶሮን ነበር - በፌዝ እያስካካና ክንፎቹን እየሰበቀ "አቶ አይጥ ይህ ነገር ላንተ የመቃብር ምልክት ይመስለኛል፣ ለኔ ምንም ለውጥ ስለማያመጣ የምጨነቅበት አይደለም" ብሎት መሬት መጫሩን ቀጠለ።

በመቀጠል ወደ በጉ ሮጠና "ቤቱ ውስጥ የአይጥ ወጥመድ አለ!" ሲል ነገረው፤ በጉ በሃዘኔታ እያየው "በጣም አዝናለሁ - እኔ ምን አገባኝ? ከመፀለይ በስተቀር የማደርገው ምንም ነገር የለም። ምስኪኑ አቶ አይጥ በፀሎቴ ውስጥ ግን እንደማልረሳህ እርግጠኛ ሁን" አለው። ከዚያም አይጡ እየተቻኮለ በቅርብ ወዳለችው ላም ሄዶ "ቤቱ ውስጥ የአይጥ ወጥመድ አለ" አላት። ላሚም ቅዝቅዝ እንዳለች "ዋው ልጅ አይጥ፤ ወጥመድ ታዲያ ለኔ ምንድን ነው? ጫፌን የማይነካ ጉዳይ ስለሆነ በእውነት የማዝነው ላንተ ነው" በማለት መለሰችለት። በመጨረሻ ከግቢው እንስሳት ያላስጠነቀቀውን ፈረስ ፈልጎ አገኘው። ፈረስ ግን ሊሰማውም አልፈለገ፣ አንገቱን መኖው ላይ እንዳቀረቀረ በዝምታ አለፈው።

የዛን እለት እኩለ ለሊት ላይ ከሽሽሽ የሚል ድምጽ ቤቱ ውስጥ አስተጋባ። ድምጹ የአይጥ ወጥመድ ሲፈናጠር የሚያሰማው አይነት ነበር። የገበሬው ሚስት ከእንቅልፏ እንደባነነች ወጥመዱ መያዙን ለማረጋገጥ ሄደች። ጭራው በወጥመዱ የተያዘው ግን ቬኖመስ የተባለ አደገኛ እባብ ነበርና እግሯ ላይ ነደፋት። ገበሬው በአስቸኳይ ሚስቱን ይዞ ወደ ሆስፒታል በረረ። ሲነጋጋ ወደ ቤት የተመለሰችው ሚስት ከፍተኛ ትኩሳትና ማንቀጥቀጥ ነበራት።

በሁላችንም ዘንድ እንደሚታወቀው ትኩስ የዶሮ ሾርባ ትኩሳትን ለማስታገስ ሁነኛ መፍትሄ ነው ይባላልና ገበሬው ወጣ ብሎ ዶሮውን በማረድ ሾርባው ተዘጋጀ። ይሁን እንጂ የገበሬው ሚስት አልተሻላትም። መታመሟን የሰሙ የቅርብ ጎረቤቶች፣ ዘመድና ወዳጆች ለጥየቃ እየመጡ ቤቱን ሞሉት። ገበሬው ለሚስቱ ሾርባና እንግዶቹን ለማስተናገድ ተጨማሪ ስጋ ስላስፈለገው በጉን አረደው። የገበሬው ሚስት ህመሟ እየጠና መድህኗ እየራቀ ቆይቶ በመጨረሻ አረፈች። በርካታ ሰው በቀብር ሥነ ስርአቱ ላይ ለመገኘትና ለማስተዛዘን ተሰበሰበ። አባወራው ከሚወዳት ሚስቱ የሚበልጥ የለምና ላሚቱን አርዶ ሃዘንተኛውን ሸኘበት። ይባላል።

አዎን . . . አይጡ ገና በጊዜ ከጉድጓዱ አጮልቆ ሲመለከት በከፍተኛ ሃዘንና ድንጋጤ ነበር። የግቢውን እንስሳትም ፈጥኖ አሳውቋል። ከቁብ የቆጠረው ግን የለም። ከዚህ ታሪክ የምንማረው ቁም ነገር አንዳችን ችግር ሲገጥመን ወይም አደጋ ሲያንዣብብን እኔ ምን አገባኝ? እኔን አይመለከተኝም! አልያም እስካልደረሰብኝ ምን ቸገረኝ? በሚል ሰበብ የተለከፍን ፍጡራን በቀጥታም ይሁን በተዘዋዋሪ ልንነካ እንደምንችል ለማሳየት ነው።

ሁላችንም ህይወት በተባለ አንድ የዘመን ባቡር ውስጥ የተሳፈርን፣ በርካታ ነገሮችን የምንጋራ ሰዎች ነን። አንዳችን መከራ ሲደርስብን ሁላችንም በአደጋ ምህዋር ውስጥ እንዳለን መገንዘብ ይኖርብናል። ሰው በመሆናችን ብቻ ያንዳችን ህመም ሊያመን፣ ያንዳችን ጉዳት ሊሰማን፣ ያንዳችን ጥቃት ሊቆረቁረን ይገባል። እርስ በእርሳችን መረዳዳት፣ መደጋገፍ፣ በንቃት አሻግረን መጠባበቅና በጠንካራ ድር እንደተሸመነ ስጋጃ ህብር ፈጥረን ጥቃትን መመከት ይገባናል። "ነግ በኔ" ምንኛ ሃያል ቃል መሰላችሁ።

ምንጭ - የሥነ ምግባርና ቀስቃሽ ጽሁፎች ድረ ገጽ
STORIES TO MAKE YOU THINK 67 Moral Stories Collection -
"The mouse trap "
ደራሲ - ያልታወቀ
ኅዳር - 27 2008 - አዲስ አበባ



## <u>ማነው ደስተኛ ?</u>

በአንድ ሠፊ ጫካ ውስጥ የሚኖር ቁራ ነበር። ዘወትር ፈጣሪውን እያመሠገነ መላ ሕይወቱን በፍጹም እርካታና ደስታ እያጣጣመ ይኖራል። ከእለታት በአንዱ ቀን ከሸለቆው በታች ዝቅ ብሎ በመብረር ላይ ሳለ አንድ ነጭ ዳክዬ ከወንዙ ጥግ ሲዋኝ ይመለከትና ንጣቱ ስላስገረመው ተጠግቶ ለማየት በቅርበት ከነበረው ቁጥቋጦ ላይ አረፈ። ከዚያም በግርምት የራሱን ጥቁረት ከዳክየው ነጭ ገላ ጋር እያወዳደረ በሆዱ “እንዴት ያምራል? በዓለም ካሉ አእዋፋት ሁሉ ደስተኛው ይህ መሆን አለበት“ በማለት አሰበና ይህንኑ ለማረጋገጥ ወደ ዳክዬው ተጠግቶ አድናቆቱን ገለፀለት።

ዳክየውም - “እርግጥ ብለሃል በዓለም ካሉ አእዋፋት ሁሉ ደስተኛው እኔ እንደሆንኩ አስብ ነበር፣ ነገር ግን ባለ ሁለት መልኩን ቆንጅዬ ፓሮት ካየሁ በኋላ ከሁላችንም በላይ ደስተኛው እሱ እንደሆነ አመንኩ” በማለት ነገረው። ቁራውም የራሱን ጥቁር ገላ ክፉኛ መፀየፍ ጀምሮ ስለነበር ይህንን ጉዳይ እስከ መጨረሻው ማዎቅ አለብኝ በሚል መንፈስ ፓሮትን ማሰስ ጀመረ። ሲፈልግ - ሲያፈላልግ ቆይቶ በሁለተኛው ቀን ከአንዷት የዛፍ ቅርንጫፍ ላይ ተቀምጦ አገኘውና ጊዜ ሳያባክን “በዓለም ላይ ካሉ አእዋፋት ሁሉ ደስተኛው አንተ መሆንህን ሰማሁ” አለው። ፓሮትም - “በዓለም ካሉ አእዋፋት ሁሉ ደስተኛው እኔ ለመሆኔ አልጠራጠርም ነበር፣ ይሁን እንጂ ፒኮክ የተባለችውን እጅግ የምታምር ወፍ ካየሁበት ቀን ወዲህ እንደዚያ ማራኪ ውበት ከተጎናፀፈች ወፍ ጋር የራሴን መልክ ሳወዳድር እፍረት ይሰማኛል” ሲል የፒኮክን ከማንም በላይ ደስተኛነት አስረዳው። አያይዞም . . . “ፒኮኮችን ለማግኘት በየጫካውና በየዱሩ እንዳትደክም፣ የሚገኙት በእንስሳት ማቆያ (Zoo) ውስጥ ነው” በማለት አከለበት።



ቁራ - ፒኮኮችን አያቸው ግን በሰዎች ተከበው ነበርና ሰዎቹ እስኪሄዱ ለብዙ ሰአት ጠበቀ። በመጨረሻ ነጠል ብላ ወደቆመችው ፒኮክ ተጠጋና በአክብሮት "ከእአዋፋት ሁሉ ውብና የበለጠ ደስተኛ የሆንሽው አንቺ በመሆንሽ የተሰማኝን አድናቆት ልገልጽልሽ እወዳለሁ! በእውነት የምታስቀኚ ነሽ" በማለት ሠላምታ አቀረበላት።

ፒኮክ መልስ ከመስጠቷ በፊት በዝምታ ተውጣ እንደተከዘች ለበርካታ ሰከንዶች ቆየች፣ ከዚያም ቀና ብላ "ውበት ምንድን ነው? ደስታስ? ውጫዊ መልክ የትኛውንም ያህል ቢያምርና ቢያንፀባርቅ ለተመልካቹ ዓይን ካልሆነ ለባለቤቱ ምን ይፈይዳል? ለእንደኔ አይነቷ ምስኪን ደግሞ ለስቃይ የሚዳርግ የህይወት ጠንቅ ከመሆን አያልፍም። እንደምታየው እድሜ ልኬን በግዞት የሽቦ አጥር ውስጥ ታስሬ እንደ ልጅነቴ ሳልጫወት - ሳልቦርቅ፣ ሳልሮጥ የምኞቴን ሳላደርስ፣ የፍላጎቴን ሳላገኝ፣ ከልደቴ እስከ ሞቴ እዚሁ ተዘግቶብኝ መኖሬ ከሁሉም የበለጠ ደስተኛ? ወይስ ሃዘንተኛ? ያሰኘኛል። የምታስቀኚ ነሽ ነው ያልከኝ? በእውነት እኔም ሆንኩ ወገኖቼ ፒኮኮች የምናስቀና አይደለንም። የምታስቀናውስ አንተ ነህ። እድሜ ዘመንህን በፈለከው ሰዓት፣ ወዳሰኘህ አቅጣጫ ከአጽናፍ እስከ አጽናፍ በተዘረጋው ሰማይ ላይ እንዳሻህ ብትበር ከልካይ የሌለብህ፣ ሜዳና ተራራውን፣ ሸለቆና ጋራውን እንደልብህ በነፃነት የምትፈነጭባቸው፣ ሲሻህ ብትሮጥ - ሲያምርህ ብትከንፍ፣ የምድር አዛዡ ናዛዡ የሌለብህ እድለኛ አንተ ነህ!። ውብና ቆንጆ አንተ ነህ!። ማማርህ ላንተ ሆኖ የምትጠቀምበት የራስህ ራስ . . . " ቃላቷን ሳትጨርስ በሃዘን ተውጣ ዝም አለች። ዝም!። ከዚህ ሌላ ምን ትበል?።

ወዳጆቼ ፦ ስንቶቻችን ነን ያለንን ጠንቅቀን የምናውቅ? እጃችን ላይ ባለው የምንኮራ? የተሰጠንን የምንጠብቅ? የሌላን ብቻ በማድነቅ፣ በመካብና በማሞገስ ተለክፈን፣ የኛ የሆነውን ሁሉ አርክሰን ራሳችንን ዝቅ አድርገን በመውረድ በገዛ አስተሳሰብና ድርጊታችን የፍጥኝ የታሰርን ሞኞች። እንደ ቁራው የታደልነውን ውበት ያልተገነዘብን እጅግ፣ እጅግ . . . ብዙ ነን። ኧረ! እንደውም ባትቆጡኝ ቁራው ስለራሱ ሲያወራ አልሰማነውም እንጂ ሌላው ሌላው ነገሩ ሁሉ የኛን የኛን መሰለኝ። የምናወራውና የምናደርገው ለየቅል እየሆነ ድንግርግሩ ከከፋ ዘመን አስቆጠረ። እንዲህ እንደ አሁኑ ተው የሚል፣ ጉድፍ የሚጠቁም፣ ፋና የሚያመላክት . . . በሳሳበት ዘመን እየባሰብን እንዳይሄድም ስጋት አለኝ።

ጥቁር ቀለም፣ ጥቁር መልክ፣ ጥቁር ነገር ስለምን ጥቁር ውበት አይሆኑም?። እውን ሰይጣን ጥቁር ነው? ሞትስ? አማልክቶቻችን ሁሉ ነጭ ስለመሆናቸው ምን ማስረጃ አለ?። ለሃዘን ጥቁር ለብሰን ለሰርግ ነጭ፣ ከቀናት መሃከል ሰኞን ጥቁር ቀብተን አርብን ነጭ። አስከፊ የሆነብንን ነገር በጥቁር መስለን ያስደስታል የምንለውን ነጭ ማድረግ ያሳደረብን ተጽእኖ እንዲህ ቀላል አይደለም። የሚገርመኝ ግን በጥቁር ሊሞዚን መንፈላሰስ የኩራት ጣርያ ተደርጎ መወሰዱ የኛ ስላልሆነ ይሆን?።

የራስን መልክ ከመጥላት የከፋ ውርደት የለም። ለራሳችን የምንሰጠው ቦታ ዝቅ ሲል ከሌላ ማነሳችንን እያመንን፣ በሽንፈት እየተጠቃን እንመጣና የኛ የሆነውን ሁሉ ወደመናቅ ይገፋናል። የቀለምና የዘር መድሎ ያሳረፈብን ሰፊ ተጽእኖ የበታችነት ስሜት እንዲያድርብን ትልቁን ሚና ቢጫወትም ጫናውን ከምንም ሳይቆጥሩ ከማንም እንደማያንሱ በተግባር ያስመሰከሩ የበርካታ ጥቁር ጀግኖችን ፈለግ መከተልና እኛነታችንን አክብረን ማስከበር ግድ ይለናል።

ሁላችንም የሉሲ ልጅ . . . ልጆች ነን፣ ሉሲ ደግሞ ነጭ ሳትሆን ጥቁር ናት። ስለ ቀዳሚው የሰው ዘር መገኛና ጥንታዊ ታሪክ ባለቤትነታችን እያወራን፣ ቅኝ ገዢ ባእዳንን ቀድመን ድል ስለመምታታችንና ስለጀግንነታችን በሰፊው እየለፈፍን፤ በየቆንስላዎቻቸው በር ላይ ተኮልኩለን አገራቸው እንድንገባ ስንለማመንና ህይወታችንን እስከመሰዋት ደርሰን በየብስም በባህርም የመንጎዳችን ነገር የምንናገረውና የምናደርገውን እንቆቅልሽ አድርጎታል።

ባለን አለመመካትና በራስ ያለመተማመን መንፈስ እየበረታ ሲመጣ ከዚህ የባሰ ዝቅተትም ይከተላል። የራስ የሆነን ሁሉ ማጣጣል፣ ሰበብ መለጠፍና አቃቂር ማውጣት። ከትንሽ እስከ ትልቅ የውጭ በሆነ አስተሳሰብና ቁስ መማረክ፣ ማድነቅና ማወደስ፤ ብሎም አንዱን ከአንዱ ደባልቆ ባለመለየት የራስን ፈልጎ እስከማጣት ሊደርስ ይችላል። ስለዚህ እኛነታችን ጠውልጎ ሳይጠፋ፣ መገለጫችን ሳይደበዝዝ ከወዲሁ ዓይናችንን ከፍተን ዙሪያ ገባችንን ልንቃኝና ባሉን እሴቶች ልንኮራ ይገባል። ከማንም እንደማናንስ ለራሳችን በመንገር፤ በጥንካሬአችን ማመንና በስብእናችን ከማንም በላይ መመካት ይኖርብናል። አለበለዚያ እንደ ቁራው ሁሉም ከኛ የተሻለ ደስተኛ፣ ሁሉም ከኛ በላይ መልከኛ እየመሰለን ስንንከራተት ልንኖር ነው።

ምንጭ - http://www.storieslerningwhatmatters.org
("Who is Happy?" or "The Peacock and the Crow")
መስከረም 2006 ዓ. ም. * አዲስ አበባ



## የ "ቆሻሻ ጫኝ መኪኖች ህግ"



(The law of the garbage truck)

ከወራት በፊት ታክሲ ተሳፍሬ ወደ አውሮፕላን ማረፍያ እጓዛለሁ፣ ከሾፌሩ ጎን ተቀምጬ ስለአለቱ የአየር ሁኔታ፣ ስለ መንገዱና ሌላም ሌላም ነገሮች እያወጋን የመንገዱን ቀኝ ጠርዝ ሁለተኛ መስመር ይዘን በመሄድ ላይ ነበርን። በድንገት አንድ ጥቁር መኪና ከማቆምያው ስፍራ ተስፈንጥሮ ከኛ ትይዩ በፍጥነት እየገሰገሰ መጣ - እጅግ አስደንጋጭ። የታክሲው ሾፌር ፍሬኑን ግጥም አርጎ በመያዝ ጎማው አስፋልቱ ጎዳና ላይ ተንሸራቶ ሲቆም፤ በአንዷት ጋት ርቀት ሳተን።

በተቀመጥኩበት ክው ብዬ ቀረሁ፣ አላበኝ፣ እንደማንቀጥቀጥም አደረገኝ። የጥቁሩ መኪና አሽከርካሪ አንገቱን በመስኮቱ አስግጎ የስድብ ናዳ አወረደብን። የኔው ታክሲ ሾፌር ግን ፈገግ ብሎ እጁን በማወዛወዝ ሰላምታ ሰጠው። እንዴት ነው ነገሩ? በእውነት የወዳጅነት ነው? ሁኔታው ግራ አጋባኝ።

"ስለምን እንዲህ አይነት ምላሽ ሰጠህ? ይህ ሰው ፈጅቶን ነበር፣ መኪናህን ድምጥማጧን አጥፍቶ  እኛን ወይ ወደ ሞት ወይ ወደ ሆስፒታል ሸኝቶን ነበር። አንተ ግን ሰላምታ ሰጥተኸው አረፍክ። ለምን?" በማለት ጠየኩት።

"በፈገግታ ሠላምታ የሰጠሁትማ በ "ቆሻሻ ጫኝ መኪኖች ህግ ምክንያት ነው" አለኝ። አልገባኝም? ፊቴ ላይ የሚታየውን ግርታ አስተዋለና ቀጠለ። ስለ "ቆሻሻ ጫኝ መኪኖች ህግ ሰምተህ ታውቃለህ? ፈረንጆቹ (The law of the garbage truck) ይሉታል፣ ካላወቅህ ልንገርህ"  በማለት እንደሚከተለው አስረዳኝ።

"ለምን ግር እንዳለህ ገብቶኛል፣ ቆሻሻ ስለሚጭኑት ግኡዝ መኪኖች እንጂ በየቦታው የምንጥለውን ቆሻሻ ሌት ተቀን ሰብስበው በማስወገድ እጅግ በከበረ ሥራ ላይ የተሰማሩትን አሽከርካሪዎች አይደለም። ልብ በል የሚመስሉትም አእምሯቸው በማይረቡ ወይም በማይጠቅሙ የሃሳብ አይነቶች ከተሞላባቸው ሰዎች ጋር ነው። ቆሻሻ በጫነ መኪና የሚመስሉ ሰዎች ከመኪናው የሚለዩት የሚጭኑት

የቆሻሻ አይነት አለመዳሰሱ ብቻ ነው። እነዚህ ቆሻሻ የጫኑ ሰዎች ቀን ከሌት በየመንገዱ የጫኑትን ቆሻሻ እንደተሸከሙ ሲዘዋወሩ ነው የሚውሉት - በርካታ ጭንቀት፣ ብዙ ብዙ ብስጭት፣ የተነባበረ ቁጣ፣ እጥፍ ድርብ ጥርጣሬና ብሶት . . . እላይ በላይ እየከመሩ ይቆዩና ጢም ብሎ ሲሞላባቸው ጭነታቸውን የሚያራግፉበት ስፍራ ይፈልጋሉ።

ታድያ አግበስብሰው ለጫኑት የብሶት ቆሻሻ ሁነኛ ማራገፍያ የሰው ልጅ ነውና ካጋጠምካቸው ማንንም ከማንም ሳይለዩ ላይህ ላይ ይደፉብሀል። ዋናው ነገር ባንተ ላይ የተነጣጠረ የግል ጥቃት አድርገህ አትውሰደው - በአፀፋው ፈገግ ብለህ እጅህን በማወዛወዝ መልካሙን ተመኝላቸው። ይህንን ከአደረክ እነሱ ሌላ ማራገፍያ ፍለጋ ሲቅበዘበዙ አንተ ወደ ሥራህ ትሄዳለህ። ነገር ግን ጀሮ ሰጥተህ ቆሻሻቸውን ካራገፉብህ አንተም ማራገፍያ ፍለጋ እቤትህ፣ ሥራ ቦታህ፣ በየመንገዱና በየደረስክበት ስትባክን፣ አልባሌ የነገር ክምር ስትጭን፣ ያለአግባብ በሰዎች ላይ ስትበትን መክረምህ ነው። የ "ቆሻሻ ጫኝ መኪኖች ህግ" ይህን ይመስላል" በማለት አብራራልኝ።

እኔም ይህን የመሰለ ጣፋጭ ወግ ያሰማኝን ትሁት የታክሲ ሾፌር አመስግኜ በመሰናበት ወደ ጉዳዬ አቀናሁ። አእምሮዬ ግን ርቆ ሄዶ በርካታ የእለት ተእለት ጉዳዮችን ያሰላስል ነበር። ለካንስ እንዲህ በየቦታው አጉራው ጠናኝ ባዮች፣ ያለምክንያት ተንኳሾች፣ በትንሽ በትልቁ ተሳዳቢዎችና ዘላፊዎች፣ የተሸከርካሪ አደጋ መንስኤዎች፣ በሥርአተ አልበኝነት ሕግና ደንብ ተላላፊዎች . . . ወዘተ ከማለዳ እስከ ምሽት የሚያንከወከዋቸው የጫኑት ቆሻሻ ኖሮዋል?።

በራሳቸው ጥፋት ደርሰው ቱግ ይላሉ፣ ከህፃናት እስከ ጎልማሶችና የእድሜ ባለፀጋ አዛውንቶችን ሳይለዩ ከአንደበታቸው በሚወጣ ፀያፍ ቃልና ምልክት ይሳደባሉ፣ ያዋርዳሉ፣ ያሸማቅቃሉ። ቁጣና ድንፋታ ይቀናቸዋል፣ ያለምክንያት ይተነኩሳሉ፣ ከፍጥነት ወሰን በላይ ያሽከረክራሉ፣ የጡሩንባ ድምጽ ያሰማሉ፣ መንገድ ዘግተው ሰላማዊውን እግረኛና አሽከርካሪ በማበጥ ረብሻና አተካራ ይፈጥራሉ . . . ወዘተ ጥፋቶችን ይፈጽማሉ። ወደው አይደለም እንደዚህ እንዳበደ ውሻ የሚያናክሳቸው የተሸከሙት ቆሻሻ ነው። እንደዚህ የሚያደርጋቸው ማልደው ከቤት ሲወጡ ጀምሮ የጫኑት እኩይ ቅዠት፣ ብሶት፣ ብስጪት፣ ቅናት፣ እልህና ዝባዝንኬ ነገር ከውስጥ እየገፋቸውና ጭነቱ እየከበዳቸው ማራገፍያ ፍለጋ ነው። አስተውሉና በትእግስት እለፏቸው።

ወዳጆቼ ፦ ለእግረኞች ቅድምያ የማይሰጥ፣ በራስ ወዳድነት ታውሮ - ደርቦ የሚያሽከረክር፣ አስፈፃሚዎች ካላዩት ለህሊናው የማይገዛ፣ ሕግና ደንብ ሲጥስ ቅንጣት የማይቆረቁረው ዳተኛ . . . ሲያጋጥማችሁ - አተኩራችሁ እዩት እሱ ከቆሻሻ ተሸካሚዎቹ አንዱ ነው። ልታይ ልታይ ባይ፣ ትምክህተኛ፣ ትህትና ያልጎበኘው፣ ለሰብአዊ ፍጡር ደንታ ቢስ፣ ሰው መሳይ የህይወት መቅሰፍት . . . ሲያጋጥማችሁ እሱም ውስጣዊ ባህሪውን በድርጊት በመግለጽ ላይ የሚገኝ ሌላው ቆሻሻ የከበደው ከንቱ ነውና በደንብ አስተውሉት።

<u>**ልብ በሉ !**</u> - በዚህ አይነት ሁላችንም ከነቃንባቸውና መድፊያ ከነፈግናቸው በምንም በማንም እስኪሰክኑ፣ ቆሻሻቸውን እንዳዘሉ ላያቸው ላይ በሰብሶ እንዲያልቅ ማድረግ አይሳነንም። ለጊዜው አንዱ የመገላገያ መፍትሄ ይኸው ነው።

ካቆሻሻ መራገፊያነት ይሰውረን! ለቆሻሻ ተሸካሚዎቹ ፍጡራንም ልብ ይስጣቸው!

ደራሲ ፦ ዴቪድ ጄ· ፖሊይ - DAVID J. POLLAY
ምንጭ ፦ The law of the garbage truck pdf book
ታህሳስ - 2006 ዓ. ም. አዲስ አበባ





"የህይወት ድልድይ"

በግብርና የሚተዳደሩት ሁለት ወንድማማቾች ከወጣትነታቸው ጀምሮ ጎን ለጎን ተያይዞ የተንጣለለ እርሻቸውን እያረሱ፣ ከብቶች እያረቡና ንቦች እያነቡ ይኖሩ ነበር። እነኝህ ጎረቤትም ቤተሰብም ሆነው የሚኖሩ ታናሽና ታላቅ ወንድማማቾች የእርሻ መሳርያና ማሽኖችን እየተዋዋሱ፣ በሚገጥማቸው ጉዳይ ላይ እየተወያዩና እየተማከሩ ከአርባ ዓመት በላይ የተሳካ ህይወት ሲመሩ ቆዩ።

ይሁንና የረጅም ጊዜ ህብረታቸው ተናጋ፣ እንከን አልባ ፍቅራቸው ንፋስ ገባው። በትንሽ ነገር የተፈጠረ አለመግባባት አድጎና ተወሳስቦ ወንድማማቾቹን ለያያቸው። መራር ቃላት በመለዋወጥ ሆዳቸውን ያሻከረው ፀብ ውሎ ሲያድር ፍጹም ለመተያየትም የማይፈልጉ ጠላቶች አድርጓቸው አረፈ።

አንድ ቀን በማለዳ የታላቅ ወንድምየው ቤት ተንኳኳ። ከእንቅልፉ የባነነው አቶ ዮሃንስ ፈጠን ብሎ በሩን ከፈተ። ድግን መጋዙን ትከሻው ላይ አድርጎ የመገልገያ ቦርሳውን በእጁ ያንጠለጠለ አናፂ ከፊት ለፊቱ ቆሟል።

“ጤና ይስጥልኝ ጌታየ! እኔ አናጺ ነኝ፣ ሥራ በመፈለግ ላይ ነበርኩ። ምናልባት አነስ ያለም ቢሆን የምሠራው ማንኛውን አይነት ሥራ ካለ ልረዳዎት ዝግጁ ነኝ።” አለው።

አሰብ አድርጎ “አ ው ው አለኝ። አንተ ልትሰራው የሚገባ አንድ ሥራ አለኝ!”። አለውና ይዞት ወደ ውጪ ወጣ። “ወዲያ ማዶ ከጅረቱ ባሻገር ያለው እርሻ ይታይሃል?” አለው በጣቱ እየጠቆመ “ያ ቦታ የጎረቤቴ . . . እውነቱን ለመናገር የታናሽ ወንድሜ ነው። መሃከላችን ያለው መሬት ከጥቂት ሳምንታት በፊት የሚያምር መስክ ነበር። ታድያ ምን ያደርጋል ይኸው ተንኮለኛ ወንድሜ ቡልዶዘሮቹን አሰማርቶ አፈሩን ቁልቁል ከወንዙ ከፍታ በታች አጥልቆ በማስቆፈር የምታየውን አዋሳኝ ጅረት ፈጠረ። አዎ! ይህ ሁሉ እኔን ለማበሳጨት ያደረገው እኩይ ሥራ እንደሆነ አውቄአለሁ። እናም ይብስ የሚያቃጥለውን አንድ ነገር ለማድረግ ተዘጋጅቻለሁ”። በማለት ሲነግረው ከፉኛ ተቆጥቶ ነበር።

ከዚያም ወደ ሌላ አቅጣጫ ወሰደውና አንድ የምርት ማከማቻ መጋዘን ውስጥ የተከመረ ጣውላ እያሳየው “በዚህ ጣውላ ቁመቱ ሁለት ሜትር ተኩል የሆነ ረጅም አጥር እንድትሰራልኝ እፈልጋለሁ። በምንም አይነት የዚያን ሰው እርሻም ሆነ ፊቱን ዳግም ማየት አልፈልግም” በማለት የሥራውን ዝርዝር አሳወቀው።

አናጺውም ”ሁኔታውን በሚገባ ተረድቻለሁ ጌታዬ! አሁን ምስማሮችና የቋሚ ጉድጓድ መቆፈሪያ ያለበትን ቦታ ብታሳየኝ ሥራውን ለመጀመር ዝግጁ ነኝ” አለውና አቶ ዮሃንስም የእቃዎቹን ቦታ አሳይቶት እንዳበቃ አንዳንድ ጉዳዮችን ለመከወን ወደ ከተማ ወጣ። አናጺው በመላ ሃይሉ ስራውን ጀመረ። ይለካል፣ ይቆርጣል፣ ይቆፍራል፣ ምስማር ይመታል . . . ቀኑን ሙሉ በጠንካራ መንፈስና በአስደናቂ የሞያ ብቃት ሥራውን ሲያከናውን ላየው መቼም የአራት ሰው ያህል ነበር። በዚህ አይነት ሲሠራ ውሎ ጀንበሯ ዘቅዘቅ ስትል አመሻሽ ላይ ልክ አቶ ዮሃንስ ከከተማ ውሎው ሲመለስ አጠናቆ ጨረሰ።

የአጥሩን ሥራ ለመመልከት በፍጥነት ከመኪናው ወርዶ ወደ ቦታው ይራመድ የነበረው አቶ ዮሃንስ ባለበት ክው ብሎ ቆመ። ማመን አልቻለም፣ አይኖቹ በሰፊው ተከፍተው፣ ከንፈሩን ቁልቁል ጥሎ በደመነብስ እየተራመደ ተጠጋ። ምንም አጥር የለም . . . አጥር የሚባል ነገር አልተሰራም። በቦታው ከወዲህ በመነሳት ጅረቱን ተሻግሮ ወዲያኛው መሬት ላይ ያረፈ የእንጨት ድልድይ ተዘርግቷል። እንከን የማይወጣለት ድልድይ። ምቹ የመወጣጫ ደረጃዎች፣ በጥንቃቄ የተሰካኩ የጣውላ መረማመጃዎችና የሚያምር ቅርጽ ያላቸው የጎንና ጎን የእጅ ድጋፎች፤ እጹብ ድንቅ የሚያሰኝ ሥራ። . . . ደግሞ ሌላ አስገራሚ ነገር - ታናሽ ወንድሙ ከወዲያኛው ጥግ እየተራመደ ወደነሱ ይመጣል፣ ፊቱ በፈገግታ ብርሃን ተሞልቶ ሁለቱም እጆቹ ወደላይ ተነስተዋል። በጥቂት ደቂቃዎች ውስጥ የተቀያየሩት ሁኔታዎች ገበሬው አቶ ዮሃንስን በእጅጉ አስደንቀውታል . . . "ያንን ሁሉ ነገር ብየህ አንተ ግን ይህንን የህይወት ድልድይ ሰራህ? በእውነት ነው የምልህ አንተ ለዚህ ተግባር የተመረጥክና ፍጹም ብቃት ያለህ ጓደኛ ነህ" በማለት እያመሰገነው ወደ ወንድሙ አቅጣጫ ተራመደ። ሁለቱ ወንድማማቾች ከድልድዩ ወዲህና ወዲያ ጫፎች ቆሙ። ከዚያም በዝግታ እየተራመዱ ልክ መሃል ላይ ሲደርሱ በደስታ ተቃቅፈው ተሳሳሙና ትከሻ ለትከሻ እንደተያያዙ የናፍቆታቸውን ይጠያየቁ ጀመር። የጥላቻ ጉድጓድ አላገዳቸውም - የአንድነት ድልድይ አገናኛቸው፣ የፀብና የተንኮል ጅረት አላለያያቸውም - የይቅርታ ድልድይ መልሶ አዋሃዳቸው።

ወንድማማቾቹ አናጺውን ለማየት እጅ ለእጅ እንደተያያዙ መጡ። አናጺው መጋዙን ግራ ትከሻው ላይ አድርጎ፣ የመሳሪያ ቦርሳውን በቀኙ በኩል እንዳነገበ ለጉዞ እየተሰናዳ ነበር። ታላቅ ወንድም ድንግጥ ብሎ - "አንተ ሰው አትሂድ . . . አትሂድ ! እባክህ? ለጥቂት ቀናት እዚህ ቆይ? በርካታ እቅዶችና ሥራዎች አሉኝ፣ እፈልግሃለሁ" ሲል ወንድምየውም ቀበል አድርጎ "እኔም ለብዙ ጉዳዮች እፈልግሃለሁ! አትሂድ ?" በማለት ተማፀነው።

አናጺው - "ጌቶቼ እዚህ መቆየቱን እወድ ነበር፣ ከናንተ ጋር ብከርምም አልጠላም። ነገር ግን ገና የማገንፃቸው ብዙ ብዙ ድልድዮች አሉ። ልሰራቸው የሚገባኝ ሥፍር ቁጥር የሌላቸው መሻገሪያዎች ይጠብቁኛልና መሄድ አለብኝ።" በማለት ተሰናብቷቸው ጉዞውን ቀጠለ። ይባላል።

<u>ወዳጆቼ :-</u> እንዲህ ያለ አናጺም አለ? . . . አጀብ ነው!። ታሪኩን ሳነብ ከድልድዩ ስር እያደር የሚሰፋው ልዩነታችን ታየኝና የኛዎቹን አናጺዎች ተግባርና ውሎ ለመመዘን በምናቤ ማደን ጀመርኩ። ምኑን ከምን ልያዝ ድብልቅልቅ ሲሉብኝ ጊዜ በሁለት ጎራ ከፋፍየ ላስቀምጣቸው ተሰናዳሁና ቡድናቸውን ለመሰየም ሳስብ ቀለል ያሉ መጠሪያያዎች መጡልኝ። አናጺ እና መናጢ፤ በዛው. . . ልቀጥል ነው።

<u>አናጺ</u> - የሚለው ቃል ደረቅ ትርጉሙ ልዩ ልዩ የእንጨት ሥራዎችን የሚሰራ፣ ለሰው፣ ለእንስሳትም ሆነ ለግኡዝ ነገሮች መጠለያ የሚያበጅ - የሚያንጽ ማለት ነው (በድሮ ጊዜ ቤት ከእንጨት ስለሚሰራ ይሆናል)። <u>መናጢ</u> - ደግሞ የእርኩሰት ባህሪይ ሲሆን ልቡ ለበጎ ነገር የማይተጋ ፣ አታላይ ፣ ተንኮለኛና ዋሾ እንደማለት ነው።

እንደ ባለታሪኩ ያሉ መለያያ አጥር እንዲያቆሙ ታዘው መገናኛ ድልድይ የሚሰሩ፣ በማቃቃር ምትክ ማግባባትን፣ በማጋጨት ቦታ ማስማማትን የሚያኖሩ። እውነትን ዘርተው፣ መዋደድን አምርተው፣ ልዩነትን አጥብበው፣ አንድነትን አስፍተው፣ በይቅርታና በምህረት ወጀብ አጽድተው ሰላምን የሚያሰፍኑ አናጺዎቻችንን ፈልጌ ፈላልጌ ከአናጺው መደብ ደለደልኳቸው። እጅግ ጥቂት ናቸው።

በሌላው ወገን መቆራረጫ የእንጨት አጥር እንዲመቱ ሲታዘዙ እይታ እስኪደፍን ጥቅጥቅ አድርገው ሲያበቁ ላዩን አሹለው አደገኛ ሽቦ የሚጠመጥሙ። ቀላል አለመግባባትን አግዝፈው፣ በቂምና ርካሽ ጥላቻ ከሽነው የሚያፋጁ። የሃሰት ድር አድርተው የተረሳ ጠባሳ አመርቅዘውና በቀል ዘርተው ግጨት ላማጨድ ሌት ተቀን የሚባዝኑትን እኩዮች ብዙም ሳልደክም አግኝቼ በመናጢው ጎራ ሰበሰብኳቸው። ለመቁጠር የሚያታክቱ በርካታ በመሆናቸው መላወሻ እስኪጠፋ ተጣበው ተከማቹ። የመናጢዎቹ ብዛት ከአናጺዎቹ አስር እጥፍ በላይ ሆነ!። ይኸው ነው እንግዲህ በጎ አሳቢው አንሶ፣ ተቃራኒው ሞልቶ ሲተርፍ ነገር . . . አለ! የሚያሰኘው። የዋዛ ይመስላል እንጂ እጅግ የሚያሳስብ ጉዳይ ነው፣ እናም የአናጺው ተግባር አናጺዎቻችንን (የኛን መናጢዎች) ቢያስታውሰኝ፤ እንዲህ - እንዲህ የሚል - ስንኝ አስቋጠረኝ . . .

**<u>አናጺው</u>**

አንተ የቤቴ ቀያሽ - የመጠለያየ አናጺ
አንተ የውሌ መሃንዲስ - የህልውናዬ ቀራጺ
ቀኑን ስናፍቅህ ውዬ - ሌቱን ተኝቼ የማልምህ
የዘወትር ሰቀቀኔ - ሳላይ ሳታዬኝ ወደድኩህ
በሥራህ ብቻ ተማርኬ - በሰሚ ሰሚ አደነኩህ
አንተትኑ ብየ አበከሬ - ሳንተዋወቅ ተመኘውህ

በሃቅ ሜትር ለክተህ - በእውነት መዶሻ ቀጥቅጠህ
በእርቅ መጋዝ ገዝግዘህ - በጽናት ምስማር አስማምተህ
ጠማማውን ከቀጥታ - ጉርዱን ከረጅም አዋቅረህ
የፍቅርን ጎጆ የምትሰራ - እርጉም ከብሩክ አዋደህ

አንተ የቤቴ መሃንዲስ - የመጠለያየ አናጺ
አንተ የውሌ ቀያሽ - የህልውናዬ ቀራጺ

ሃሰት ፈብርኮ የሚያባላ - ዋሽቶ ማስታረቅ ቀርቶበት

የበቀል ሳማ ተካዩ - ቂም የሚዘራ በሞላበት
ተንኮል ሸርቦ የሚያፋጅ - ፈጥሮ የሚያጋጭ በፈላበት
እሳት ላይ ነዳጅ ቸላሹ - ፀብ የሚያጋግል ባየለበት

አጥር ሲታዘዝ መለያያ - ድልድይ የሚያንጽ መገናኛ
እንደ በረከት የሚታደል - ያንድነት መሲህ ታምረኛ

ሲያሻኝ ስጠይቅ ሳጠያይቅ - ስባጅ ስፈልግ ሳፈላልግ
ስመኝ ስናፍቅ ስንገበገብ - ሳስስ ስፈትሽ ከጥግ ጥግ

ከልጅ ካዋቂ ከሴት ወንዱ - ከምሁር ማይም ከያንዳንዱ
ከላይ ታች ብየ ቆጠርኳቸው - እፍኝ አይሞሉም ያየኋቸው

ዳኛ መካሪ አስታራቂ - የፍቅር ሚዛን ባለ ራእይ
እኩል የሚወድ ማያዳላ - የሚያስተሳስር ይቅር ባይ
ያገር የወገን ሽማግሌ - ነፍሱን በስጋው የማያሞኝ
የማይቀላምድ የማይሸሽ - ባስቀመጡበት የሚገኝ
እውነት ሰባኪ ሃቀኛ - እንዳሻኝ እንደናፈቀኝ
እንዳንተ ያለ አናጺ - የሚበጀኝን ሳላገኝ
እንዳለምኩ እንደተመኘሁ - ጭጋግ ዘገና ሆኖብኝ
ዘመን አለፈ ገሰገሰ - ስባትት ቀረሁ እንዳማረኝ

ኧረ ዳኛ መካሪ - እኔስ አናጺ አምሮኛል
አለሁ አለሁ ባይ መናጢ - ዙሪያየን ከቦ ይዞኛል
መሻገርያዬን የሚያድስ - እንዳንተ ያለ ይለኛል
እኔስ አናጺ አምሮኛል - ከቶ ከወዴት ይገኛል ?።

ምንጭ ፡ Social Media - Collection of Moral Stories
Roger Darlington's World and 72 thoughtful stories
"Bridges Of Life" or (The two brothers)
ደራሲ፡ ያልታወቀ * ጥቅምት - 2007

"ቅዱሳን ከ ኃጥአን"



አባ አንስታስዩስ የታላቁ ገዳም ኃላፊ ናቸው፣ ቦታው ግብጽ አሌክሳንደርያ። ዘመናትን ያስቆጠሩ፣ የትም የማይገኙ፣ እጅግ ብርቅና ውድ የሆኑ መጽሃፍትና የጥበብ ውጤቶች በገዳሙ ክፍሎች ውስጥ ሥርአት ይዘው ተደርድረዋል። ከእለታት በአንዱ ቀን ገዳሙን በመንብኘት ላይ የነበረው መነኩሴ በሚያየው አስደናቂ ስብስብ ተመስጦ ከቆየ በኋላ አንድ እርኩስ ሃሳብ ሽው ሲልበት ስጋዊ ፍላጎቱ አሸነፈው፤ ወዲያ ወዲህ አማትሮ አንዱን ውድ መጽሃፍ አነሳና በስተጀርባው ቀሚሱ ስር ሸሽጎት ወጣ።

ተጠርጣሪውን አድኖ መያዝ ከባድ አልነበረም፣ ሌባው እለቱኑ ታወቀ። ይሁን እንጂ አባ አንስታስዩስ እንዲሳቀቅም ሆነ በጭራሽ አልወሰድኩም ብሎ እስከመማል እንዲደርስ አልሻምና ማንም ተከታትሎ እንዳይይዘው በማለት ከለከሉ። ከዚህ በኋላ መነኩሴው መጽሃፉን የሚገዛው ሰው ማፈላለግ ጀመሮ ብዙም ሳይቆይ ቀናውና አንድ ሃብታም ሰው አገኘ። ሰውየውም ሊገዛው እንደሚችል ነገር ግን ለመመርመርና ዋጋውን ለመተመን አንድ ቀን ስለሚያስፈልገው መጽሃፉን ትቶለት እንዲሄድ ጠየቀው፣ እርሱም በመስማማቱ አስቀምጦለት ሄደ።

መነኩሴው እንደወጣ ሃብታሙ ሰው መጽሃፉን ይዞ ወደ ገዳሙ ሄደና ለአባ አንስታስዩስ አሳያቸው። አባ ገና እንዳዩት ነበር ያወቁት፤ ግን ምንም አላሉም። "ይህንን መጽሃፍ ከአንድ መነኩሴ ልገዛው ነበር" በማለት ቀጠለና "ውድ ስለሆነ በወርቅ ገንዘብ ነው የምሸጥልህ ብሎኛል። በዚህ በኩል የእርስዎን ያህል የካበተ እውቀትና ችሎታ ያለው አይገኝምና እንዲያረጋግጡልኝ ነው ያመጣሁት ?" በማለት ጠየቃቸው።

አባም "ከጠየቀህ ተመን እጅግ . . . እጅግ የላቀ ዋጋ ያለው፣ ከበርካታ የወርቅ ገንዘቦችም በላይ የሚያወጣ ድንቅ መጽሃፍ ነው" አሉት። ሃብታሙ ሰው የገዳሙን ኃላፊ አመስግኖ ወደ ቤቱ አቀና። በቀጠሯቸው መሰረት በቀጣዩ ቀን ከመነኩሴው ጋር ሲገናኙ መጽሃፉን ሊገዛው እንደወሰነና የጠየቀውን የወርቅ ገንዘብም በማዘጋጀት ላይ እንደሆነ ነገረው። መነኩሴው በጣም ተደሰተ። አያይዞም . . .

"ግን ማን መረመረልህ?፣ ለማን ነበር ያሳየኸው?" በማለት ጠየቀው።

"አባ አንስታስዩስ - የገዳሙ ኃላፊ" በማለት መለሰለት።

መነኩሴው ደነገጠ! ዞረበት። ፊቱ እየገረጣ ሲሄድ አመድ የተነሰነሰበት መሰለ።እንደምንም እየተንተባተበ "እ . . . እ እና . . . ምን አ ሉ?" አለው።

"መጽሃፉ የወርቅ ገንዘብ ሊያወጣ እንደሚችል አረጋገጡልኝ"

"እ . . . እና ሌላስ ? "

"ሌላ . . . ምንም"።

መነኩሴው ለመግለጽ በሚያስቸግር ስሜት ተዋጠ፣ የሚለውና የሚያደርገው ጠፋው። አሰበ . . . "የገዳሙ ኃላፊ መጽሃፉን ለማስመለስም ሆነ ወንጀለኛውን ለማስያዝ አልፈለጉም። እጃቸው የገባውን ንብረት እና የሚያሳስሩትን ሌባ አውቀው ትተዋቸዋል። ከዚህ በኋላ በሌብነቱ የሚከሰውና የሚከታተለው ሰው የለም፣ ነፃ ነው። እንደዚህ ያለ ምህረትና እውነተኛ ፍቅር፣ እንደዚህ ያለ መውደድና ይቅርታ አይቶ አያውቅም። በሕይወት ዘመኑ ውስጥ ማንም ማንም እንደዚህ አስጠግቶትና ቀርቦት አያውቅም" በጥልቀት አሰበ አሰበና . . . ገባው፣ ሁሉንም ተገነዘበ።

ድንገት ብድግ ብሎ መጽሃፉን ከጠረጴዛው ላይ አፈፍ አርጎ አነሳ። "ይቅርታ - ሃሳቤን ቀይሬአለሁ! ሃሳቤን ቀይሬአለሁ" በማለት እቅፍ አርጎ ያዘው።

ግራ የተጋባው ባለሃብት (መጽሃፍ ገዥ) "የወርቁን ገንዘብ እጨምራለሁ፣ ሁለት . . . ሦስት . . . እሺ አራት "እያለ በጉጉት ይጮህ ጀመር። መልስ የለም . . . መነኩሴው በሩን ዘልቆ በፍጥነት ይራመዳል፤ ጉዞ በቀጥታ ወደ ገዳሙ ኃላፊ፣ ወደ አባ አንስታስየስ ገሰገሰ . . . ቁና ቁና እየተነፈሰ በፍጥነት እንደመራመድም፣ እንደመሮጥም እያደረገው ትልቁን መግቢያ ተሻግሮ ወደ ውስጥ እንደገባ ፊት ለፊት አያቸው። መጠነኛ ወንበር ላይ ተቀምጠዋል። ዳግም ቀና ብሎ ሊያያቸው ድፍረት አጣ፣ እንዳጎነበሰ ተራመደ፣ ቆመው ጠበቁት፣ ፍጹም ብሩህ ፈገግታ ይነበብባቸዋል። መጽሃፉን እጃቸው ላይ ሲያስቀምጥ እንባው ቁልቁል መጽሃፉና ጣቶቻቸው ላይ ተንጠባጠበ . . . እፎይ።

"እንካ ያዘው፣ ውሰደው" አባ አንስታስየስ ተናገሩ "እኔ እንደተገነዘብኩህ ተውሰህ ነበር የወሰድከው፣ አሁን ደግሞ ልሸልምህ ወሰንኩ፤ ውሰደው" አሉት።

መነኩሴው ተንበረከከ፣ ማልቀሱ ብሶበት እየተንሰቀሰቀ ለመናቸው "እባክዎን ይያዙት፣ ይቀበሉኝ መጽሃፉን ይውሰዱና የምለምኖትን አንድ ነገር ብቻ ያዳምጡኝ፣ አባቴ! እዚሁ ተቀምጬ መልካም ሥነ ምግባርን ከእርስዎ እማር ዘንድ ይፍቀዱልኝ!"። በማለት እየተንቀጠቀጠ ለመናቸው።

እንደተመኘው ጥያቄው ይሁንታ አገኘና በገዳሙ ውስጥ መኖር ጀመረ። ከእኒህ የተባረኩ ሰው በየእለቱ እውቀት እየቀሰመና እየተማረ፣ በጣፈጠ መንፈሳዊ ሕይወት ተከቦ ቀሪ እድሜውን በሙሉ በገዳሙ ውስጥ አሳለፈ። የምንግዜም ምሳሌውና መምህሩም አባ አንስታስየስ ነበሩ። ይላል በቅርብ ከ አንድ የሥነ ምግባርና ኃይማኖታዊ ትምህርቶችን ከሚያዘጋጅ ድርጅት ድረ ገጽ ላይ ያነበብኩት ታሪክ።

አባ አንስታስዬስ የገዳም ኃላፊ ናቸው፣ እጅግ ድንቅ የሆነው አመለካከታቸውና የአመራር ጥበባቸው፤ የውስጣዊ እምነታቸው ነፀብራቅ እንጂ የገዳም መሪ ስለሆኑ አልያም በውስን ገደብ ለሃይማኖታዊ ተቋም ብቻ የሚያገለግል ጽንሰ ሃሳብ አይደለም። እንደ እርሳቸው ያለ አስተዳዳሪ፣ የህዝብና የመንግስት ተጠሪ፣ መሪ፣ ሹምና . . . ወዘተ ቢኖረን ምን ይለናል።

ግዴለም እንደ እርሳቸው ያለ (አባ . . . ) ሲያምረን ይቅር፣ እሱን ትተን እስቲ ሌላውን እንይ። ብዙ ብዙ ነገር ይሰረቃል፣ ይጠፋል ወይም የገባበት አይታወቅም። ያ ማለት ከጠፋው ነገር ጋር የሚመጣጠን ሰራቂ፣ ሌባም በሉት ወሳጅ መኖሩ ግድ ነው። ስንቱ ይጋለጣል?፣ ስንቱ ይያዛል? ስንቱ ይረጋገጥበታል ወይም ምን ያህሉ ይፈረድበታል? ሰንጠረዡን ለባለሞያዎቹ አስቀምጠን መሬት ጠብ የሚለውን ሃቅ ብንመዝን ያስተዛዝባል ብቻ አይገልፀውም። ጭንቅላት አስይዞ ያስጮሃል ።

ስርቆት እጅግ ፀያፍና አስነዋሪ ተግባር ነው። ሌብነት ክፉና አሳፋሪ አመል ነው። በጥቅሉ የሚያስቀጡ ወንጀሎች መሆናቸው እንደተጠበቀ ሆኖ እንደነዚህ አይነቶቹን ድርጊቶች ለመቀነስ፣ ለማክሰምና ለመቆጣጠር በህግ አግባብና በአስፈፃሚ አካላቱ ብቻ የሚወሰዱ እርምጃዎች በቂም ፍቱንም አይደሉም እላለሁ። ይልቅስ ማህበረሰቡ ሲያወግዛቸው፣ የእውነት ሲፀየፋቸውና ሲያነውራቸው በራሳቸው ይኮማተራሉ፣ ይጫጫሉ፣ ይሳሳሉ። ተራፊዎቹን በሕገ ደንቡ ማስተናገድ እዳው ገብስ ነው። የአስፈፃሚ መሥሪያ ቤቶችንና የባልደረባዎቻቸውን እፎይታም አንድ በሉና ከዚህ አንፃር በሰዎች አእምሮና አስተሳሰብ ላይ ቢሰራስ በእውነት ታላቅ ለውጥ ሊያመጣ የሚችል ያልተቃኘ ምእራፍ ነው፤ ቢታሰብበት?።

የገዳሙ ኃላፊ የተጠቀሙበት ዘዴና ትእግስት እንደወረደም ባይሆን በሚመሳሰሉ አይነቶችና ብልሃቶች ጥቅም ላይ ሊውል ይችላል። ህሊናን የሚኮረኩር ፀፀትና ከውስጥ ያሚመነጭ ይቅርታ ያላቸውን ፋይዳ ይጠቁማል። የሰው ልጅ ከእስር ከግርፋት . . . ወዘተ ከመሳሰሉት የቅጣት አይነቶች በላቀ ደረጃ ስብእናውን የሚነካና ከዳግም ወንጀል ፍጹም የሚያፀዳ እርማት ምን ማለት እንደሆነም አየን።

ምንጭ፡ Swayamsat Meet Yourself (Institute of Clinical Hypnosis and Related Sciences PLC) - "Saint and Sinner"
ሃምሌ - 2008 * አዲስ አበባ

## ውግያ !

መምህር ነኝ ከሦስት ሳምንት በፊት በአንድ የከተማችን ዩኒቨርሲቲ ኮሌጅ ውስጥ የሚደረገውን ውድድር እንድዳኝ በቀረበልኝ ጥሪ መሰረት ወደ እዚያው አመራሁ። አዳራሹ በሰዎች ተሞልቷል፣ የኮሌጁ መምህራንና ተማሪዎች፣ ወላጆችና ተጋባዥ እንግዶች ስፍራ ስፍራቸውን ይዘዋል። እኔም ለዳኞች በተዘጋጀው ቦታ ከሌሎቹ ባልደረቦቼ አጠገብ ተቀመጥኩ። ከፊት ያሉትን ሁለት ረድፎች ሞልተው የተቀመጡት ሁሉም ተሳታፊዎች የታደላቸው ወረቀት ላይ አተኩረዋል። ወረቀቱ ንግግር የሚያደርጉበትን ርዕስ ጉዳይና የተሰጣቸውን የሦስት ደቂቃ የጊዜ አጠቃቀም በአጭሩ የሚያስረዳ ነበር። ተወዳዳሪዎቹ በቀጣዩ አመት የሚመረቁ የዩኒቨርሲቲው ተማሪዎች ሲሆኑ ውድድሩ በተለያዩ ጉዳዮች ላይ ያላቸው ግንዛቤና የማስረዳት ብቃት የሚመዘንበት ነበር። ቀዳሚው ተናጋሪ ማን ይሆን፣ የሚቀጥለውስ፣ ከዚያስ . . . እያሉ በጉጉት ሲጠባበቁ ቆይተው የሥም ጥሪው ሲጀመር በፀጥታ መከታተል ጀመሩ። የመጀመሪያውን ተናጋሪ መቼም ቢሆን አልረሳውም። ገና ወደ መድረኩ ሲወጣ በራስ ያለመተማመንና የመረበሽ ስሜት ይነበብበት ነበር። አትራኖሱን ደገፍ ብሎ ቆመና ከፍ ባለ ድምጽ መናገር ጀመረ . . .

“የተከበራችሁ ዳኞችና ውድ ተማሪ ጓደኞቼ! ይህ ፍትሃዊ ውድድር አይደለም!፣ ይህንን በማለቴ አዝናለሁ” ሲል እኔና አብረን የተሰየምነው ዳኞች በግርምት አስተዋልነው። ልጁ ንግግሩን ቀጠለ ”ንግግር የማደርግበትን ርዕሰ ጉዳይ የሚገልፀው ይህ የምታዩት ወረቀት አሁን ስለተሰጠኝ ለመዘጋጀት የነበረኝ ጥቂት ደቂቃ ብቻ ነው። ከኔ በኋላ የሚያቀርቡት ልጆ ች ግን ስለሚናገሩት ነገር ለማሰብ በቂ ጊዜ ያገኛሉ፣ ይህ በፍጹም ትክክል አይደለም፣ አድሎ ነው!” በማለት ተቃውሞውን ገለፀና ከመድረኩ በመውረድ አዳራሹን ለቆ ወጣ። በመውጣቱ ያዘነም ሆነ ያኀደለው ነገር አልነበረም፣ ውድድሩ በጥሩ ሁኔታ ተከናውኖ በስኬት ተጠናቀቀ።

ልጁን ለማነጋገር ስለፈለኩ ፈጠን ብዬ ወጣሁና ከመንገዱ በስተቀኝ ጠርዝ ላይ ቆሞ አገኘሁት። ፈገግ ብዬ “ሕይወት ፍትሃዊ ናት ያለህ ማነው?” አልኩት። ግራ በመጋባት ትኩር ብሎ አየኝ፣ ወደ መኪናዬ እንድንሄድ ጠይቄው ጎን ለጎን እየተራመድን ወጋችንን ቀጠልን . . .

“ሕይወት ዘወትር ከ ኢ-ፍትሃዊነት ጋር እየተፋለመች፣ ላለመረታት እየታገለችና ላለመውደቅ እየቆመች በማሸነፍ መራመዷን ለአፍታም ሳታቋርጥ ሁሌም በሂደት ላይ የምትገኝ ነች” አልኩትና “የአውቶሞቢል ኩባንያ መጽሄቶችን ታነባለህ?” በማለት ጠየኩት።

“አዎን - አነባለሁ” ሲል መለሰልኝ።

“በጣም ጥሩ - አንድ አዲስ መኪና ተመርቶ ገበያውን ለመቀላቀል የሚያስተዋውቁበትን መንገድ አስተውለሃል? የሚናገሩት ስለ ምቾትና ፍጥነቱ ነው፣ የሚያብራሩት ስለ ሞተሩ ጥንካሬና የፈረስ ጉልበቱ መጠን ነው። ይሁን እንጂ እንዲህ በሚደረድሯቸው አሃዞች ውስጥ አንድ የማይታይ መስመር አለ። ምን መሰለህ - የፍጥነቱ፣ የጉልበቱም ሆነ የጥንካሬው ጥናትና ልኬት የተመዘነው በተዋጣለት የመንገድ ደረጃና በምቹው አካባቢያዊ ሁኔታ ውስጥ ነው። እስቲ ስለ ምቹ መንገዶች አስብ?” በማለት ማስረዳቴን ቀጠልኩ ልጁም ራሱን በመነቅነቅ መስማማቱን ገለፀልኝ። “የሚመስጠው ማስታወቂያ መኪኖቹን ከበቂ በላይ ያሸጣቸዋል - ይሁን ተሸጡ። ወደ ዋናው ጉዳይ ስመጣልህ አንሸራታች፣ ጎርበጥባጣና በጭቃ የተሞሉ መንገዶች ላይ በአስቸጋሪ የአየር ፀባይ ውስጥ የተወሳላቸውን የፍጥነት፣ የምቾትና የጥንካሬ ብቃት ይዘው ይቀጥላሉ ወይ? የሚለው ነው። መልሱ አዎ! ይወጡታል። በለስላሳው የአውሮፓ ጎዳና ላይ መፍሰስ በኮረኮንቹ የአፍሪካ መንገድ ላይም እየተንገጫገጩ መጓዝ አይገዳቸውም። ጃፓን ተመርተው የኢትዮጵያን መጋቢ መንገዶች ማጥ በጣጥሰው ይወጣሉ። ምቾትና ፍትሃዊ ዳኝነትን ከችግርና አድሎኣዊ አሰራር ጋር እኩል ቦታ ላይ ማስቀመጥ፣ መዳኘትና ማሸነፍ ማለት እንደዚህ ነው።

ለጥ ባለ አስፋልት መንገድ በሰዓት 240 ኪሎ ሜትር ፍጥነት እንዲበሩ የሚያደርጋቸውን ኃይል ሲታደሉ፣ አጓጉል ዳገትና አዘቅት ላይ ተንቀባረው የሚራመዱበት ልዩ ጥርስ ተገጥሞላቸዋል። ምቾት የተላበሰው ውስጣዊ ክፍላቸው በሚያንደላቅቅ ወንበርና በተመጣጠነ አየር ሲደራጅ፣ ድንገተኛ አደጋን የሚከላከል ቀበቶና የንፋስ ከረጢትም ተዘጋጅቶላቸዋል።

እኛ የምናሽከረክራቸው ሰዎች ይህንን ስለምናውቅ እንደ ችግሩ ሁኔታ አስፈላጊውን ቁልፍ በመጫን አፈትልከው እንዲወጡ እናደርጋቸዋለን። ነገር ግን ይህ ብቃት እኛ ዘንድ እንዳለ ስለማንረዳ ወይም እርግጠኞች ስላይደለን ሁሌ የተደላደለ ሁኔታና የተመቻቸ የውድድር ሜዳ እንጠብቃለን።

አንተ የመጀመርያው ተናጋሪ መሆንህን እንደ አጋጣሚ ሳይሆን አድሎ እንደተደረገብህ አድርገህ ወስድክ፣ የመጨረሻው ተናጋሪ ብትሆን ኖሮስ ፍትሃዊ ነው ትላለህ?። ከዚያም ከተመደበልህ 3 ደቂቃ ወይም 180 ሰከንዶች ውስጥ ለ 20 ሰከንዶች ብቻ ተቃውሞህን በማሰማት ጥለህ ወጣህ። የቀረህን ጊዜ ከምታባክን የቻልከውን ያህል ብትሞክር እንኳ የተሻለ ነበር። አስገራሚው ነገር የውድድሩ አሸናፊ ካንተ ቀጥሎ የተጠራው ልጅ መሆኑን ስነግርህስ ምን ይሰማሃል?”።

እንዲህ እየተነጋገርን መኪናዬ አጠገብ ደረስን . . .

“የኔ ልጅ! ምን ጊዜም ሁኔታዎችን በምቹና በተደላደለ ጎናቸው ብቻ አትገንዘብ። ሕይወት እንደመንገዱ በጎርበጥባጣ መሰናክሎች የተሞላችና ኢ-ፍትሃዊ ሳንካዎች የተንሰራፉባት መስክ ነች። ሞክር፣ ተጋፈጥ፣ ተቋቋምና ድልን ተቀዳጅ። አለመመጣጠንና ኢ-ፍትሃዊነት ትናንትም ነበረ፣ ዛሬም አለ፣ ወደፊትም ይቀጥላል። በአሸናፊነት ለመዝለቅም የማያቋርጥ ትግልና ያላሰለሰ ጥረት ግድ የሚሉ ናቸው” በማለት ምክሬን አካፍየው ተሰነባበትን። እኔም መኪናየን አስነስቼ ሄድኩ። በፈገግታ ተሞልቶ እጆቹን ሲያውለበልብልኝ በኋላ ማሳያው መስታወት አየሁትና ደስ አለኝ። ከዛሬ ጀምሮ ኢ-ፍትሃዊነትን መዋጋት ይጀምራል። ይህ ገሃድ ሃቅ የተጋረደባቸውና እውነታውን ያልተረዱ በርካታ ወገኖቼም ትዝ አሉኝ።

የሕይወት ፈተናና የኑሮ ውጣ ውረድ ምንግዜም የሚገቱ አይደሉም። እስቲ በአለማችን ላይ ተሳካላቸው የተባሉ ሰዎችን እንጠይቅ?። የስኬታቸው ምስጢር በፍትሃዊም ሆነ በኢ-ፍትሃዊ ሁኔታዎች ውስጥ፣ ትክክልም ሆነ አድሎአዊ በሆነ ፈተና ስለመዳኘታቸው ቁብ ሳይሰጡ የታገሉና በአሸናፊነት ነጥረው የወጡ ናቸው። ስለ ውጊያው ፍትሃዊነትና ኢ-ፍትሃዊነት ለራሳችንም ሆነ ለአለም በማውራት ጊዜአችንን አናጥፋ። ያ ሳንጀምር በተስፋ መቁረጥ ከፍልሚያው ሜዳ ያስወጣናል። በአንፃሩ ቆርጠን እንግባበት፣ በጽናት እንጋፈጥና የአሸናፊነትን ድል እንቀዳጅ።

ምንጭ፡- 17 Motivational and Inspiring Short Stories www. Livin3 .com
“BATTLE OUT THE UNFAIR”
ነሃሴ - 2008 * አዲስ አበባ

## **“እ ም ነ ት”**

አንድ ተራራ መውጣት የሚያዘወትር ሰው ነበር። ይህ ሰው በየጊዜው ለብቻውም ከጓደኞቹም ጋር እየሆነ በተለያየ ቦታ በመዘዋወር እጅግ አዳጋችና ቀጥ ያሉ ድንጋያማ፣ አንሸራታች፣ በበረዶ የተሸፈኑና በጥልቅ ሸለቆ ላይ የተንጠለጠሉ ፈታኝ ተራሮችን በመውጣት ከፍተኛ ዝናን ያተረፈ ነው።

ከእለታት በአንዱ ቀን ረፋድ ላይ ገመዱንና የጉዞ ቁሳቁሶቹን ተሸክሞ አቀበቱን ተያያዘው። እንደ ግንብ ቀጥ ብለው የተነባበሩትን አለቶች እያለፈ ካሰበው ሰዓት አርፍዶ ተራራው ጫፍ ላይ የደረሰው ምሽት ላይ ነበር። ደመናው ጨረቃና ከዋክብቱን ስለሸፈናቸው ሥፍራው ድቅድቅ ጨለማ ውጦታል። እንቅስቃሴው ሁሉ በዝግታና በተጠና ጥንቃቄ ሆኖ ወደ ፊት ተራመደ - 1 . . 2 . . በሶስተኛው እርምጃ ግን ያልታሰበ አስደንጋጭ ክስተት ተፈጠረ፤ አንሸራተተው . . . ቁልቁል ተምዘገዘገ፣ በአየር ላይ ተንሳፍፎ የቆየ መሰለው። በሽርፍራፊ ሰከንዶች እእምሮው ስለ ሞት፣ በህይወቱ ስለፈፀማቸው ጥሩና መጥፎ ነገሮች፣ በዝብርቅርቅ ሃሳቦች ተወጠረ።

ወደ ታች በፍጥነት እየተወረወረ የነበረው ሰውነቱ በድንገት ወገቡ ላይ በነበረው ገመድ ሲሸመቀቅና በቀዝቃዛው አየር ላይ ተንጠልጥሎ ሲወዛወዝ አንድ ሆነ። ያልተጠበቀ ተአምር ነው፤ ስለመትረፉ አሰበ። ሌላ ድንጋጤ፣ ሌላ ሰቀቀን የህይወቱ መጨረሻ መላ ክብደቱን አንጠልጥላ በያዘችው ገመድ ጥንካሬ ላይ አርፏል።

ከ ፈጣሪ አምላክ በስተቀር ከዚህ መአት ሊያወጣኝ የሚችል ማንም የለም ሲል አሰበና “አምላኬ እርዳኝ”. . . “ጌታየ እርዳኝ”. . . እያለ ደጋግሞ ይጮህ ጀመር። በድቅድቁ ጨለማ ውስጥ የገደል ማሚቶ ከሚደጋግመው የራሱ ድምጽ መሃል እንደነጎድጓድ የሚያስተጋባ ድምጽ ሰማ።

“ምን እንድረዳህ ትፈልጋለህ?” አለው።

“አምላክ ሆይ አድነኝ” “አምላክ ሆይ አድነኝ” ሲል ተማፀነ።

የሚያስገመግመው ድምጽ “በእውነት እኔ እንደማድንህ ታምናለህ ?” ሲል ጠየቀው።

“በሚገባ አምናለሁ ጌታዬ! ትችላለህ ! ታድነኛለህ አምላኬ!” እያለ ጮኸ።

“እሺ አድንሃለሁ። በል . . . ወገብህ ላይ የተጠመጠመውን ገመድ ቁረጠው” ሲል አዘዘው።

ንግግር የለም። ከሚያፏጨው ንፋስ በስተቀር ምንም ድምጽ አይሰማም። ፀጥ - እረጭ፤ ከደቂቃዎች በኋላ ሰውየው ገመዱን በሁለቱም እጆቹ ግጥም አድርጎ ያዘ። መላ ሃይሉን በማጠናከር ገመዱን የሙጥኝ እንዳለ . . . ቆየ . . . ቆየ . . . ቆየ . .

በቀጣዩ ቀን ስለ ተራራ ወጪው ሰው የተለያዩ ወሬዎች ተናፈሱ። ከአንዱ ወደ አንዱ እየተቀባበለ እየተጨመረና እየተቀጠለ መላ መንደሩን አዳረሰው። ረፋድ ላይ በሰበር ቀጥታ ስርጭት የተላለፈው ዜና ግን እንደሚከተለው ሁሉንም ያሳዘነና እጅጉን አስገራሚም ነበር።

የአካባቢው ፖሊስ የድንገተኛ አደጋና የነፍስ አድን ቡድን ስለ አደጋው ይፋ ባደረገው ሪፖርት . . . . **“አደጋው በደረሰበት ስፍራ ተራራ ወጭው ገመዱን በእጆቹ አጥብቆ እንደያዘ በቅዝቃዜ ደርቀ ህይወቱ ያለፈ ሲሆን አስከሬኑም ከመሬት 35 ሳ. ሜትር ከፍታ ላይ ተንጠልጥሎ እንደተገኘ በምርመራ ተረጋግጧል ሲል ይገልፃል”**።

ከመሬት በላይ 35 ሳንቲ ሜትር = (አንድ ክንድ ብቻ)



እምነት - እምነት ነው !። ከአምላክ ቃል በላይስ ምን ሊታመን ነው? እስቲ ስንቶቻችን ነን ገመዱን የምንቆርጥ? ስንቶቻችንስ ነን ገመዱን እንኳን ልንበጥስ እጅግ አጥብቀን የምንይዝ? በእውነት ገመዱን ለመበጠስ የሚበቃ የማያወላውል ጽኑ - እምነት በውስጡ

ያለው (ያላት) ከተገኘ ምንኛ የሚያስቀና ባህሪ የታደለና ጠንካራ ሰው ነው (ነች)። ይህ የሁላችንም የጋራ ድክመት ቢስተካከል፣ በፈጣሪያችን ላይ ያለን እምነት የማያወላውል፣ በእውነት ላይ የፀናና የተረጋገጠ ቢሆን ኖሮ፤ ሁሉም ነገር ምን ያህል በተሳካልን ነበር።

ደራሲ :- ያልታወቀ

ምንጭ :- ከማህበራዊ ድረ ገጽ የተገኘ ታህሳስ - 2006 - አዲስ አበባ

## "ወርቅማው ቤት"

ኮረብታው ላይ የተቀለሰችው ትንሽ ቤት ዙሪያዋ ችምችም ባለ የሸምበቆ አጥር ተከቧል። የቤቷ መጎሳቆል የነዋሪዎቿን ድህነትና በአነስተኛ ገቢ መተዳደር ያሳብቃል። ብስክሌቷን ጠባቧ ግቢ ውስጥ ከወዲያ ወዲህ እየነዳች የምትጫወተው ልጅ ከህፃንነቷ ጀምሮ ከሸለቆው ባሻገር ተራራው አናት ላይ ያለውን የሚያምር ቤት ቀርባ ለማየት ትመኝ ነበር። ብስክሌቷ ላይ ሆና በርቀት የሚታያት ቅንጡ ቤት ከማማሩም በላይ ወርቅማ መስኮቶቹ የሚያንፀባርቁት ብርሃን እጅጉን እየማረካት ትኩር ብላ ስታየውና ከራሷ አሮጌ ቤት ጋር እያወዳደረች የወርቅ መስኮት ያለው ቤት ውስጥ መኖር ምን ያህል ድንቅና የአስማት ያህል እንደሚቆጠር ታስባለች።

ትንሿ ልጅ ወላጆቿን፣ ትንሽ ወንድሟንና አሮጊት አያቷን በጣም ስለምትወዳቸው በዘወትር ህልሟ ሁሉም በአንድነት በሚያምር ወርቅማ ቤት ውስጥ ሲኖሩ ይታያት ነበር። እድሜዋ እየጨመረ፣ የብስክሌት አነዳድና አጠቃቀም ችሎታዋም እየተሻሻለ ሲመጣ ከግቢው ወጥታ በቀጭኑ ጎዳና ላይ ብስክሌቷን ለመንዳት ትችል ዘንድ በየጊዜው እናቷን ፈቃድ ትጠይቃት ነበር። ተደጋጋሚ ልመናዋ ያስጨነቃት እናት በመጨረሻ ፈቀደችላትና ልጂት በደስታ እየፈነደቀች ቀጣዩን ቀን ስትናፍቅ አደረች።

ከሩቅ እያየች ስታደንቅ የነበረውን ቤት ቀርባ የምታስተውልበት ጊዜ ደረሰ። በማለዳ ከእንቅልፏ ተነስታ ወደ ደጅ ወጣች። እለቱ ደስ የሚል፣ ሰማዩ ጥርት ያለና በነፋሻ አየር የታጀበ ጠዋት ነበር። ቁልቁል ሸለቆውን አቋርጦ የሚወርደውን ቀጭን መንገድ ይዛ የተራራውን ጠርዝ በጥንቃቄ በማለፍ የወርቅማውን ቤት ዋና መግቢያ እስከታገኝ ድረስ፤ ብስክሌቷን ያለማቋረጥ ጋልባ ባሰበችው ጥሩ ሰአት ከቤቱ ፊት ለፊት ደረሰች።

ብስክሌቷን ከበሩ ማእዘን ትይዩ በተቃራኒው በኩል ደበቅ አርጋ አስቀመጠችና የቤቱን ውጫዊ ገጽታ ቀርባ ወደምታስተውልበት አቅጣጫ አመራች። በአንድ በኩል የፈራረሰውን አጥር በቀላሉ አልፋ ወደ ቤቱ ይበልጥ እየተጠጋች ስትመጣ የገዛ አይኗን ማመን አቅቷት ጨፈን - ከፈት እያደረገች አተኩራ አየችው። በግርምት እንደደነዘዘች በቆመችበት ድንጋጤ ወረራት። ምርጊቱ ያፈጠጠ አሮጌ የጭቃ ቤት። ዝናብ የሸረሸረው ቡናማ ግድግዳ፣ መልኩ ከመሬቱ ጋር ተመሳስሏል። ከልሙጥ ጣውላ የተሰሩት አመድማ መስኮቶች ውሃ እንደጠማው ጭንጫ መሬት ተሰነጣጥቀዋል። እድሜ የጠገበው የቆርቆሮ ክዳን ከላይ እስከ ታች ዝገት ተከናንቧል። የወላለቀ በረንዳ፣ እዚህም - እዚያም የተቦረቦረ ወለል፣ ዳዋ የለበሰ የአትክልት ስፍራና በቁጥቋጦ የተሸፈነ ግቢ . . . ገና ሲያዩት ያለ ባለቤቶቹ ዓመታትን እንዳስቆጠረ ያስታውቃል። አና ነው።

ልጂት ከሩቅ ሆና ዘወትር የምታየው አንፀባራቂ ባለወርቅ መስኮት ቤትና ተአምረኛው የአበባ አፀድ የለም። እንባ ባቀረረ አይኗ ከፊት ለፊቷ ተገትሮ በብዥታ የምታስተውለው ነገር ውቅያኖስ ዳርቻ የተጣለ አሮጌ መርከብ መሰላት። በተሰበረ ልብ ከዚህ በላይ መቆየት አልሆነላትም። በሃዘን እንደተዋጠች ለመመለስ ወስና ዞር ስትል ባሻገር ኮረብታው ላይ የራሷን ቤት አየች። ሌላ ተቃራኒ ግርምት! እጅግ ድንቅ ነገር፤ ትንሽዬ አፏን በትናንሽ መዳፎቿ ሸፍና እንዳፈጠጠች ቆማ ቀረች። በጠዋቷ ፀሃይ መስኮቶችዋ ወርቅማ ብርሃን የሚያንፀባርቁ የምታምር ቤት፤ አቤት ጉድ ነው!። አሁን የእውነት በወርቅማ ቤት ውስጥ እንደምትኖር ተረዳች። የምታገኛቸው ንጹህ ቤተሰባዊ ፍቅርና እንክብካቤም የወርቃማዋ ቤታቸው አብይ ድምቀቶች እንደሆኑ አወቀች። ከልጅነቷ ጀምሮ ስታልምና ስትመኝ የቆየችው ነገር ካፍንጫዋ በቀረበ ርቀት እየኖረችው እንዳለ ተጨባጨን ሃቅ ተገነዘበች።

ትንሿ ልጅ ብስክሌቷን ካስቀመጠችበት አንስታ ወደ ወርቃማው ቤቷ የመልስ ጉዞዋን ጀመረች። ሸለቆውን ተሻግራ ሽቅብ የኮረብታውን ጠመዝማዛ መንገድ ስትጋልብ፤ ህሊናዋን ለሙሉ የህይወት ዘመኗ የሚመግብ ቁም ነገር ጭናው ነበር። የልጂት ህልምና የርቀት ምኞት እያንዳንዳችን ዘንድ አለ። ልጂት በህፃን አእምሮዋ የሳለችውን ወርቅማ ቤት እኛ ከልጅነት እስከ ሽምግልናችን ስንነመኸለት እንኖራለን። እንደወርቅ እያንፀባረቀ፣ እንደ አልማዝ እያበራ፣ ወደ ራሳችን እንዳናይ በሩቅ እያማለለ እግር ተወርች ቀፍድዶናል። በቅዠት ተንሳፈን ያለ የሌለ ጥሪት፣ ጊዜና እሳቤአችንን አሟጠን ቀርበን የማየትና የማረጋገጥ እድሉን ስናገኝ ወርቁም ወርቅ አይደል፣ አልማዙም አልማዝ አልሆነ ከንቱ . . . የከንቱ ከንቱ።

እናም . . . ለዚህ "ወርቅማ ቤት" ቀጣዩን ስንኝ ቋጠርኩለት . . . አንዳንዴ የማነባቸው ጽሁፎች ግጥም እንድጽፍላቸው ይገፋፉኛል።

### የሚታይህ ከወዲያ ነው . . . !

ተስፋውን በሩቁ አንጠልጥሎ - ነገን አሻግሮ እያየ
የምኞት አድማሱን አስፋፍቶ - በአናው ቀፎ እየቆየ
በሰመመን ይባክናል - በቀቢፀ ተድላ እየጋየ
በጨለማ ይዳክራል - የሌለውን ከማያየው እየለየ

ኑሮና ግብሩን ተፀይፎ - ዙሪያ ገባውን ጠልቶታል
ውሎና አዳሩ ሰልችቶት - አጓጉል ጠረን ሸቶታል
ፍራሽ መኝታው ቆርቁሮት - ጎኑን ሰቅስቆ ይዞታል

ምቾት የነሳው መቀመጫ - ፍጹም ማረፍያ ነስቶታል

ብቻ - መጋለብ ይፈልጋል - መሮጥ መሸምጠጥ ይመኛል
መንሳፈፍ መብረሩን ይሻል - ደርሶ መፈንጠር ያምረዋል
ወደ አብረቅራቂው ተራራ - ወደ ተስፋው የሩቅ ምድር
ባሻገር ወደሚታየው - ወደ ሞላለት የሰው አገር

የወርቁን ከምር እየዛቀ - በድሎት ዘሮች ሊቀማጠል
ካልማዙ ጎታ እየዛቀ - በቅንጦት አይነቶች ሊሽልል
ብቻ - መጋለብ ይፈልጋል - መሮጥ መሸምጠጥ ይመኛል
መንሳፈፍ መብረሩን ይሻል - ደርሶ መንደርደር ያምረዋል

ያልተዘራ ላይታጨድ - ላይታፈስ ምርት አለሙ
ያላቆዩት ላይጨበጥ - ላይዳሰስ የሌት ህልሙ

ወርቁም ወርቅ አይደለ - ሽግናት ነው የሞላበት
አልማዙም አልማዝ አልሆነ - ከቶ ዝገት ነው ያጠላበት
ድግሱም ስስት ነውና - ስጋት ሰቀቀን ነው የፋፋበት
ቅንጦቱም ብክነት ነውና - ባዶ ጉራ ነው ያየለበት

የጎጆህ ብርሃን ፀዳሉ - የቀየህ ግርማና ሞገስ
የቤተሰብህ ፍቅር ዳና - ያገር የመንደርህ ቅርስ

እውነታው ሚዛን ሲደፋ - ትዝታህ ዘልቆ ሲዳረስ
የሚያኮራህ ከወዲያ ነው - ባሻገር ሆነህ ስታስታውስ
የሚታይህም ከዛው ነው - አንተነትህን ስትላበስ
የሚገባህም ያኔ ነው – ወደ ቅን ቀልብህ ስትመለስ።

የታሪክ ምንጭ፡- Roger Darlington's World - 76 thoughtful stories
"The house with the golden windows"
መጋቢት 2007 * አዲስ አበባ



**<u>የሲንዱጃ - ባልንጀራ</u>**

<u>(ጓደኝነት - 3)</u>

ህንዳዊው አባት ስለ ልጁ የፃፋት አጫር ገጠመኝ ፡-

እለቱ እሁድ ነው፣ ከሰዓት በኋላ። ወትሮ እንደማደርገው ገረፍ ገረፍ አድርጌ ያለፍኳቸውን የሳምንቱ ጋዜጦች አንድ በአንድ አነባለሁ። "ይህንን ጋዜጣ ቀኑን ሙሉ ነው እንዴ የምታነበው? እባክህ ወደዚህ ናና እቺን ልጅ አንድ በላት ምግቧን አልበላም ብላ ይኸው በረሃብ ልትሞት ነው" አለችኝ ባለቤቴ። መናደዷ ያስታውቃል። ጋዜጣዬን አስቀምጬ ወደዚያው ሄድኩ። ሲንዱ በፍርሃት ተውጣ ቁጭ ብላለች፣ ዓይኗ እንባ አቅርሯል፣ ፊት ለፊቷ ጠረጴዛው ላይ የበሰለ ሩዝ በጎድጓዳ ሰሃን ተቀምጧል። ሲንዱ ብቸኛ ልጃችን ናት፣ ዘንድሮ ስምንተኛ ዓመቷን የያዘች ቀልጣፋና ብሩህ አእምሮን የታደለች ልጅ።

ለሩዝ እምብዛም ፍላጎት እንደሌላት አውቃለሁ፣ እናቴና ባለቤቴ ደግሞ ጥቅሙን እያብራሩ ሁሌም እንድትበላ ይጫኗታል። ጠጋ ብዬ አንድ ማንኪያ ቀመስኩና "የኔ ውድ ለምን ትንሽ አትበይም? ካልበላሽ እናትሽ አንቺን ብቻ ሳይሆን እኔንም ትቆጣኛለች ያ ደግሞ ጥሩ አይደለም" አልኳት - በማባበል። ሲንዱ ረገብ አለች፣ እንባዋን በመዳፏ ጠረገችና "እሺ - እበላለሁ! ትንሽ ብቻ አይደለም ሙሉውን ጭርስ አድርጌ እበላለሁ ግን፣ አንተ የምጠይቅህን" መቀጠል ፈርታ ቆየችና . . . "ባባ ሩዙን ጥርግ አድርጌ ከበላሁ - ምንም ይሁን ምን የምጠይቅህን ነገር ታደርግልኛለህ?" በማለት ጠየቀችኝ። እኔም "በሚገባ አደርግልሻለሁ! ቃሌ ነው" አልኳት "ቃልህ ነው?" "ቃሌ ነው!" ተባብለን አውራ ጣቶቻችንን በማነካካትና በመጨባበጥ ተስማማን።

ቀና ብላ ከኋላ ወደቆሙት እናቷና አያቷ እጇን ዘረጋች በተመሳሳይ ሁኔታ ጭብጦቻቸውን በማጋጨት አረጋገጡላት። ከዚያ በኋላ ሲንዱ በዝምታ መመገቧን ቀጠለች። አጠገቧ ቁጭ አልኩና "ሲንዱዬ የምትጠይቂኝ ነገር እንደ ላፕ ቶፕና አይ ፓድ ያለ ውድ ነገር እንዳይሆን አባትሽ በቂ ገንዘብ የለውም" አልኳት። "አይደለም ባባ፣ አውቃለሁ ውድ ነገር አልጠይቅህም" አለችኝ።

ሲንዱ በእርጋታ ተመግባና ታጥባ በፈገግታ ወደ እኔ ስትራመድ የሁላችንም ትኩረት እርሷ ላይ ነበር። "ባባ እኔ የምፈልገው ዛሬ ፀጉሬን መላጨት ነው!" አለች። ሁላችንም ተያየን፣ ክው ብለን ደነገጥን። ባለቤቴ በንዴት - "አይሆንም! ሴት ልጅ በፍጹም ፀጉሯን አትላጭም! አስቃቂ ነው" በማለት ጮኸች። እናቴም በቁጣ ተነሳች "በእኛ ቤተሰብ ውስጥ ማንም አድርጎት አያውቅም፤ ይህንን ቴሌቪዥን እያየች ያመጣችው ጣጣ ነው! ምን ይሻላል? ቴሌቪዥን ባህላችንን አጠፋ! ቴሌቪዥን ልጆቻችንን አበላሸ! . . . " እያለች ተቃውሞዋን ገለፀች።

ቀስ ብየ "የኔ ቆንጆ ሌላ አይነት ነገር ብትጠይቂን ይሻል ነበር። አንቺን መላጣ ሆነሽ ማየት ምን ያህል እንደሚያሳዝነን ገምተሻል?" አልኳት በማባበል። "እኔ ሌላ ምንም ነገር አልፈልግም" አለችኝ ኮስተር ብላ - በማስረገጥ። ተስፋ አልቆረጥኩም "ሲንዱ - እባክሽን ስሜታችንን ብትረጂልን ምናለበት?" አልኳት በማስተዛዘን።

"ባባ ያን የማይጥም ሰሃን ሙሉ ሩዝ መብላት ለኔ ምን ያህል ከባድ እንደነበር ይታይሃል? ደግሞ ቃል ገብታችሁልኛል። የነገርከኝን ተረት ታስታውሳለህ? - የንጉሱ ታሪክ። ቃል የእምነት እዳ ነው! የገቡት ቃል ከሚጠፋ፣ የወለዱት ይጥፋ፣ ምንም ይሁን ምን ቃል አይታጠፍም የሚለው" አለችኝ። ዓይን ዓይኔን አተኩራ እያየች። አዎ . . . የዛ የምስራቅ አፍሪካ ጥቁር ንጉስ ታሪክ ትዝ አለኝ። ብድግ ብዬ አቀፍኳት፣ የመጨህ ተራው የኔ ሆነ "ቃላችን እንደተጠበቀ ነው! አይሻርም! አይለወጥም" አልኳት። እናቴና ባለቤቴ አሻፈረኝ አሉ፣ "አብደሃል ወይ? እንዴት ይህንን ትፈቅዳለህ በማለት ቢሞግቱኝም "ዛሬ እኛ የገባንላትን ቃል ካላከበርን በህይወቷ ውስጥ ስለ ቃል ኪዳን ጽኑነት ምን ልትማር ትችላለች" በሚል አቋሜ ረጋሁና ሲንዱ የፈለገችው ሆነ።

ሰኞ ጠዋት ወደ ትምህርት ቤት ላደርሳት ከቤት ስንወጣ ሙልጭ ተደርጎ የተላጨው ፀጉሯ ከክብ ፊቷ ጋር አይኖቿን ጎላ ጎላ ስላደረገው ሲንዱ ይበልጥ ቆንጆ ሆና ታየችኝ። መኪናዬን ከትምህርት ቤቱ ፊት ለፊት አቆምኩና ትንሿ ልጄ ለመጀመርያ ጊዜ ያን ረጅም ፀጉሯን ጥላ ወደ ክፍል ስትገባ ማየት ጀመርኩ። ዞር ብላ እጇን አውለበለበችልኝ እኔም አፀፋውን መለስኩላት።

በዚህ መሃል "ሲንዱጃ! ሲንዱጃ - ጠብቂኝ" የሚል ድምጽ ሰማሁ፣ ከኔ ኋላ ከቆመው መኪና ውስጥ የወረደው ትንሽ ልጅ ወደ ሲንዱ ይሮጣል፣ ፀጉር የተባለ የለውም መላጣ ነው። "አው ነገሩ እንዲህ ነው እንዴ?" አልኩ በሆዴ። ወዲያው አንዲት ሴት ከኋለኛው መኪና ወርዳ ወደኔ መጣች "ጌታዬ ልጅህ ታላቅ አመለካከት ያላት የተባረከች ልጅ ነች" አለችኝና ራሷን ሳታስተዋውቅ መናገሯን ቀጠለች። በጥልቅ ስሜት ውስጥ እንዳለች ያስታውቃል፣ ከመኪናዬ ወረድኩና ቆምኩ። "ያ ከልጅህ ጋር የሚሄደው ወንድ ልጅ የኔ ልጅ ሃሪሽ ነው" አለችኝ። ቀና ብዬ አየኋቸው . . . እጅ ለእጅ ተያይዘው ወደ ክፍላቸው ይራመዳሉ። ሴትየዋ ቀጠለች "ልጄ ሃሪሽ ሉኪሚያ በተባለ የካንሰር ህመም ሲሰቃይ ከርሟል" ሳግ ተናነቃትና ድምጿ ተቆራረጠ ጉሮሮዋን ጠራርጋ ቀጠለች።

"ብቸኛ ልጄ ላለፉት ወራት ህክምና ላይ ስለነበር ትምህርት ቤት አልመጣም፣ እንደምታውቀው ለካንሰር ህመም የሚሰጠው የኬሞ ትራፒ (የኬሚካል) ህክምና በሚያስከትለው ተጓዳኝ ተጽእኖ ምክንያት ፀጉሩን ሙሉ ለሙሉ አጥቷል። ከካንሰር ጋር ታግሎና አስቸጋሪውን ህክምና ተቋቁሞ እየተሻለው ቢመጣም ያለፀጉር ወደ ትምህርት ቤት መሄዱን ግን አልተቀበለውም። ተማሪ ጓደኞቹ ያበሽቁኛል፣ ይስቁብኛል፣ ያሾፉብኛል ብሎ ፈራ፣ ተሳቀቀ። በተለያየ ዘዴ ለማሳመን ሞክረን አልተሳካልንም። ይገርምሃል! ባለፈው ሳምንት ሲንዱጃ ልትጠይቀው መጣች (እሱ ሲንዱጃ ስለሚላት እኛም በዛው ነው የምንጠራት)። ለ ሰአታት ሲያወሩ ነበር፤በተማሪዎች በኩል ይደርስብኛል ብሎ ስለፈራው ነገር ሁሉ እርሷ ሃላፊነቱን እንደምትወስድና ከጎኑ እንደምትቆም ቃል ገባችለት . . ." አሁንም ሳግ አነቃት፣ የታመቀ እንባዋ ገንፍሎ ቁልቁል ይዘንብ ጀመር፣ ቀሪውን ታርክ የጨረሰችልኝ የእንባ ወጀብ እየናጣት ነበር።

"ሁለቱ ጓደኞሞች መከሩና ተስማሙ። ምን አይነት ስቃይ ውስጥ እንደነበርን ይታይህ፣ ሲንዱጃ በምንም አይነት ያንን የሚያምር ዘንፋላ ፀጉሯን ተላጭታ ለጓደኝነት ፍቅር ትሰዋለች ብየ አላሰብኩም። እግዚአብሄር ይባርካት አንተና ባለቤትህም ተባረኩ፣ ታላቅ ፀጋን የታደላችሁ ቅኖች ናችሁ" አለችኝ። እኔም ተጋብቶብኝ እንባዬን መቆጣጠር አቃተኝ።

የሃሪሽን እናት ተሰናብቼ ወደ ቢሮዬ አቅጣጫ ነዳሁ . . . የልጄ የሲንዱ ተግባር ልቤን ነካው "የኔ ትንሽ መልአክ እባክሽ አንድ ውለታ ዋይልኝ? እንደገና መወለድ ቢኖርና ዳግም ብወለድ አንቺ እናቴን ሆነሽ ጓደኝነት ምን እንደሆነ አስተምሪኝ? . . . የጓደኝነትን ዳራና ጥግ አሳውቂኝ?" አልኩ - በሆዴ።

"ዘጠና ዘጠኝ በመቶ ጥፋትና ውድቀቶች የሚከሰቱት ይቅርታና ውለታን በማያውቁ ሰዎች ነው" ይባላል።

አመሰግናለሁ! የሲንዱጃ አባት።

ሲንዱ ትንሽ ልጅ ነች፣ እድሜዋ ገና ስምንት ነው። የኔን አሰላሁ ከስድስት እጥፍም በላይ ይልቃታል። በህይወት ዘመኔ ለጓደኝነት ፍቅር የሰጠሁትን ክብርና ያበረከትኩትን አስተዋጽኦ በወፍ በረር ለማስታወስ ሞከርኩ . . . በዚህ ረገድ ራሴን የተሻልኩ አድርጌ ነበር የማስበው ግን ኢምንት ሆነብኝና ዝም አልኩ። እስቲ እናንተም ቃኙት አርጉት።

ምንጭ ፡ ከሥነ ምግባር ትምህርቶች ድረ ገጽ www.hearttouchingstory.com
18 Inspirational Stories - "WHAT IS FRIENDSHIP"
ሰኔ 10 2008 - አዲስ አበባ

## የሰብአዊነት ጣርያ

እውነተኛ ታሪክ ✱ ወርሃ ሰኔ 2007 ዓ. ም.

ቦታው አዲስ አበባ ከፒያሳ ወደ አራ በከንቱ ከሚያወርደው ጎዳና በስተግራ ገባ ብሎ ነው። ጓደኛዬ ቢያንስ በሳምንት አንድ ቀን ወደዚህች ሥፍራ ይሄድና መኪናውን ጥላ ስር አቁሞ ለተወሰነ ሰአት ማንበብ ከጀመረ ከራርሟል። የዙርያው ትእይንት ለምን እንደሆነ በማያውቀው ምክንያት እየማረከው ከመጣ ወዲህ ባጋጣሚ የተዋወቃቸው ወዳጆቹን ቢያንስ በሳምንት አንዴ በተለይ እሁድ ከሰአት እንዲጎበኛቸው የሚያስገድድ ሁኔታ ተፈጠረ።

ነገሩ እንደዚህ ነው . . . ያችን የመንገድ ዳር ጥላ ሥር የተላመደ ሰሞን መኪናው ውስጥ ሆኖ እያነበበ እግር ጥሏቸው በአካባቢው የሚያልፉና ጥላዋን ፍለጋ የሚመጡ የተለያዩ ችግረኞች እንደ መልካቸው የተለያየ ምክንያት እየደረደሩ በሚያቀርቡት ምጽዋት ጥየቃ ከንባቡ መቋርጡን ለምዶታል። እሱም ቀና እያለ እንደየ አመጣጣቸው ይሸኛቸዋል። በዚህ መሃል የአንዳንዶቹ ሁኔታ ግን ለደቂቃዎች በትካዜ ተመስጦ እንዲቆይ ያስገድደዋል። በተለይ በለበሱት አዳፋ ከነቴራና በሰለሉ ክንዶቻቸው ስር ደብቀው የያዙትን ማስቲሽ እየማጉ፣ በቀጫጭን እግሮቻቸው ህዋ ላይ እንደሚጓዝ ጠፈርተኛ እየተንገዳገዱ የሚቀርቡት ታዳጊዎች አንጀቱን ያላውሱታል። ትኩር ብሎ ያያቸዋል የሚናገሩት አይሰማም፣ እህል የራቀው አንጀት ረሃባቸውን በገደሉበት ማስቲሽ ተኮማትሮ፣ የሚረጨው አሲድ ከንፈራቸውን ኩበት አስመስሎታል። በቢጫማ ቀለም ወይበው የቦዙት አይኖቻቸው ማየት መቻላቸውን ለማረጋገጥ ይከብዳል።

አቤት! . . . መከራቸውንና መላ ያጣ የወደፊት እጣቸውን ሲያስብ ከፉኛ ይሳቀቃል። ሳንቲም ይለምናሉ ቢሰጣቸው የሚገዙት ያው ማስቲሽ ነው። በባዶ ሆድ የሚማግና እጅግ የሚሰነፍጥ፣ መርዛማ ኬሚካል። ድሮ የምናውቀው ቤንዚን ነበር ከችግሩ ጋር እሱም ጠነከረና ዛሬ ዛሬ ማስቲሽ የሚስቡ ህፃናትን ከተሞቻችን ጎዳና ላይ መመልከት የተለመደ ሆነ። አዲሱን ትውልድ የከበበው አሰቃቂ የጥፋት ደመና፣ የታዳጊ ልጆቻችን የቁም ሞት፣ የመጥፋቸው መጨረሻ ዋዜማ፣ የማሕበረሰቡ ውርደት አዋጅ፣ ሁላችንም ትኩረት የነፈግነው ሰቅጣጭ እውነት። ከቶም የማንሸሸው የእርቃን ገመናችን መደምደሚያ...ወዘተ አሰቃቂ ትእይንት። ምን ያድርጋቸው?።

ውሎ ሲያድር አንድ ዘዴ መጣለት፣ ገንዘቡ ወደ ምግብ ተቀይሮ መመገባቸው የሚረጋገጥበት ዘዴ። እነሱኑ በዝግታ እያነጋገረ አስፈላጊውን መረጃ አሰባሰበና ውሳኔ ላይ ደረሰ። ይኸውም የተቀቀለ ድንች ለሚሸጡት እማማ ዘነበች የሳምንት ቀለብ በመክፈል፣ ምግብ የሚያገኙበትን መንገድ ማመቻቸት ነበር። በአቡሽ የተጀመረው ሳምንታዊ የምግብ ድጎማ ተሳካና ዛሬ ጥቂት ታዳጊዎች በቀን አንዴ ቅቅል ድንች የሚበሉበትን ሁኔታ ፈጠረ። ጓደኛዬን በየሳምንቱ ወደ ፒያሳ የሚያስኬደው የወዳጆቹ የሳምንት ቀለብ ቅድሚያ ክፍያ ብቻ አልነበረም። ፍቅራቸውን እንዲህ ያጠናውና እሁድን የሚያስናፍቀው ነገር፤ ሌላ ሆኖ አረፈው። ምን?።

በራሱ አንደበት "አሁንማ በምንም አይነት ሳላያቸው ሳምንት መቆየት አልችልም። ምን መሰለህ ገና ሲያዩኝ ወደኔ ሮጠው ይጠመጠሙብኛል። በሳምንቱ ውስጥ ያጋጠሚቸውን በጎም ሆኑ ክፉ ገጠመኞች እየተሽቀዳደሙ ያወሩልኛል። በአራዳ ቋንቋ እያጣፈጡና በሳቅ እየተንፈቀፈቁ ይተርኩልኛል፣ እኔም ነገረ ሥራቸው ሁሉ ስለሚገርመኝ ከልብ አጅባቸዋለሁ። በዚህ በዚህ ከምግብ ይልቅ ሰው እንደሚርባቸው ተገነዘብኩ። ከቅቅል ድንች ይብስ ታላቅ ወንድም እንደሚያሻቸው አወቅሁ። አሁንማ የምናፍቃቸው እኔ ነኝ። አይናቸው ውስጥ የማየው የደስታ ፀዳል ከምንም በላይ የሚያረካኝ እኔን ነው። ምነው በኖረኝና ባበዛኋቸው እላለሁ" ያለኝን አልረሳውም።

እስከ አሁን ያወጋኋችሁ ተያያዥነት ስላለውና ታሪኩን ከስሩ ለማንሳት ያህል እንጂ በዋናነት ልተርክላችሁ የፈለኩት፣ ጓደኛዬ ጥላው ስር መኪናው ውስጥ ተቀምጦ ታዳጊ የጎዳና ወዳጆቹን ሲጠብቅ ያየውና ባድናቆት የነገረኝን አንድ አስገራሚ ገጠመኙን ነበር። እነሆ . . .

እዚያው የተለመደው ቦታ መኪናዬ ውስጥ ነበርኩ። እድሜአቸው ከአስራ አምስት እስከ አስራ ስምንት አመት የሚገመት አምስት ወጣቶች ናቸው። ከመሃከላቸው ቀጠን ረዘም ያለው ልጅ በቅባት የራስ ፌስታል አንጠልጥሏል። እያወሩና እየተሳሳቁ መንገዱን አቋርጠው ፀሃይዋን ከልሎ ጥላ ወደፈጠረው ግንብ ተጠጉ። የሁሉም አይን ወደ ፌስታሏ ያማትራል፣ ፊታቸው በጉጉት እንደበራ ክብ ሰርተው ተቀመጡ። አሁን የሚያወሩት ሁሉ በደንብ ይሰማኛል፣ ማንበቤን ሙሉ ለሙሉ አቋርጬ እከታተላቸው ጀመር።

ቀጭኑ ልጅ ፌስታሉን መሃከላቸው አስቀመጠና ዙርያ ጠርዙን በጥንቃቄ ወደ ውጭ ጠቀለለው። ሰፋ ብሎ የተከፈተው ፌስታል ያልታጨቀበት የምግብ ዘር የለም። የጾም በያይነቱ፣ ቀይ ስር፣ የተጋጠ አጥንት፣ በአልጫ መረቅ የወዛ ጥቅልል ቢጫ እንጀራ፣ ሞራና ጅማት የሚበዛበት የተተለተለ ስጋ፣ ግማሽ ጎኑ በቀይ ወጥ የተለወሰ ዳቦ፣ ቡናማ ፍትፍትና ቡራ ቡሬ ናፕኪን ወዘተ. . . ዝብርቅርቅ ቀለም፣ የስእል ብሩሽ የተጠረገበት ሸራ መስሏል። በልጆቹ ቋንቋ – "ኡፋ" የምሳ ገበታቸው ተሰናዳ። እዚህ አካባቢ እጅ በመታጠብ የሚባክን ጊዜ የለም፣ በስንት መከራ የሚበላ ተገኝቶ በቀጥታ መሳተፍ ነው። የክጀላ ምራቅ የሚያመነጩ ጉሮሮዎች ተከፈቱ፣ ረሃብ የሞረሞረው ሆድ ላይ የተሰኩ ቀጫጭን እጆች ወደ ፌስታሉ ጉድጓድ ተሰነዘሩ . . . ።

እሁድ ከሰዓት በግምት ዘጠኝ ሰዓት አካባቢ ይሆናል፣ የረፈደ ምሳ ድግስ ተጀመረ። አንድ ... ሁለት ... ሦስት፤ ምንም ንግግር የለም፣ በፀጥታ መመገባቸውን ቀጥለዋል። አንዲት እንደነገሩ የለበሰች ሴት ወደ ልጆቹ ትራመዳለች . . . ቀረበቻቸው። ሁለተኛ ጉርሻቸውን በአፋቸው ሙሉ እያላመጡ፣ ሦስተኛውን በጣቶቻቸው ያመቻቻሉ። ሁሉም ቀና ብለው አዩአት "ልጆች! እባካችሁ በልታችሁ የቀረውን ለውሻዬ ፈልጌ ነበር፣ ትሰጡኛላችሁ?" በማለት ጠየቀቻቸው።

ግራ በመጋባት ተፋጠጡ። ተርፏቸው ያውቃል እንዴ? የትራፊ – ትራፊ – ትርፍራፊ? ወይ ጊዜ። ረጅሙ ልጅ ድምጹን ከፍ አድርጎ "በቃችሁ! በቃችሁ የያዛችሁትን ብቻ ጉረሱና በቃ እንሰጣታለን" አለ። "አልጠገብንም እኮ"፣ "ገና መች በላንና ነው" . . . አጉረመረሙ። ቀጭኑ ልጅ ፌስታሉን አንስቶ ጥቅልሉን እየፈታ "አይዞሽ ሌላ ጊዜም ለውሻሽ ከፈለግሽ እንሰጥሻለን" በማለት ለሴትየዋ

ሰጣት። ተቀብላ ቦርሳዋ ውስጥ ከተተችውና እየመረቀቻቸው በተቃራኒው አቅጣጫ ተራመደች። ሴትየዋ እየራቀች ስትሄድ ወደ ጓደኞቹ ተመለከተ፣ ያኮረፉ ይመስላሉ፣ “ምን ሆናችሁ?” አላቸው።

“እኛ ሳንጠግብ ለምን ለውሻ ትሰጥብናለህ?” በአንድ ድምጽ ጠየቁት።

“አይደለም – ለውሻዋ አይደለም! ለራሷ ነው!” አለ። ሁሉም ደነገጡ፣ ቀጭኑ ልጅ ቀጠለ . . . “እሷ እንደኛ አይደለችም ታፍራለች፣ አትለምንም፣ ግን እርቧታል። እኔ አውቄአለሁ ለውሻዬ ብላ ትጠይቅና ለራሷ ትበላዋለች” አላቸው።

“የሁሉም መንፈስ ሲረጋጋ፣ ፊታቸው እርካታና ደስታን ሲላበስ፣ በሚያንፀባርቅ ፈገግታቸው ይታወቅ ነበር። ጣታቸውን እየላሱና እንደ አመጣጣቸው እየተሳሳቁ ተነስተው ሄዱ፣ ርቀው እስኪሰወሩ በአይኔ ተከተልኳቸው... አይገርምም?” በማለት ታሪኩን ነግሮኝ አበቃ። እጅግ ተመስጬ ነበር ያዳመጥኩት፣ ግሩም መልእክት አለው፤ ብጽፈው ምን ይመስልሃል? አልኩት። ትከሻውን እየሰበቀ “እንደፈለክ ትችላለህ” አለኝ። እሺ ብዬ ልጽፈው ወሰንኩና ይኸው እንደዚህ ፃፍኩት። ያሬድ ጓደኛዬ ከልብ አመሰግናለሁ!።

ቤት የለሹ፣ አይዞህ ባይ – ወላጅ አልባው፣ ሲነጋ ትኩስ ሻይ – ሲመሽ ጣፋጭ መክሰስ የማያውቀው። ካርቶን አንጥፎ፣ ድሪቶ ደርቦ – ከቀን ብርድ እስከ ሌት ቁር እርቃን አካሉን የሚጋፈጠው። መጥገብ ብርቁ፣ ርሃቡን ቢያገኝ ትርፍራፊ አልያም በማስቲሽ ቃና እያስታመመ፣ ኑሮ ብሎ ከሚኖረው የጎዳና ፍሬ – እንዲህ ያለ ጥልቅ ስብእና ከየት መጣ?።

የሰብአዊነት ጣርያው የት ድረስ ነው?። ሞልቶ የተረፈው የፈቃዱን ያህል ይለግሳ፣ ሌላው እንደ አቅሙ ይቸራል፣ ቆንጥሮ የሚመፀውትና ካለው ገምሶ የሚያካፍልም አለ። ሁሉም መስጠት ነው። ምንም ሳይኖረው ወደ ተከፈተ አፉ የሚወስደውን ጉርሻ ከኔ ይብስ ተርቧል ብሎ ወዳሰበው ሰው የሚሰነዝር፣ የምግብ አምሮቱን ቻል አድርጎ - ተቋቁሞ፣ የታጠፈ አንጀቱን ያለርህራሄ ከፉኛ ከሚቧጥጠው ጠኔ ይልቅ የሌላን ስቃይ የሚያዳምጥ ስብእና ምን ይባላል?። ለሰብአዊ ክብር የሰጠውን ቦታ እዩልኝ። ለውሻዋ ያለመሆኑን እያወቀ፣ ሴትየዋ እንዳትሰማውና ቅር እንዳትሰኝ አስቦና እስከትርቅ ጠብቆ እውነቱን ለጓደኞቹ ነገራቸው። የሌሎችን ስሜት በመጠበቅ፣ ሃፍረት፣ ዝቅተኝነትና ውርደት እንዳይሰማቸው ያደረገውን ጥንቃቄና የጨዋ ተግባር መዝኑልኝ። የጓደኞቹ ልባዊ ፈቃድና መልካም ተግባርስ ጫፉ የት ድረስ ነው? . . . ።

እውነቱን ለመናገር እነዚህን ነው ጎዳና ተዳዳሪዎች የምንላቸው። የታጠበ ስለለበስን፣ ቆርቆሮ ቤት ውስጥ ስለተኛን፣ ሽርፍራፊ ገንዘብ ኪሳችንን ስለሞላው ወይም መኪና ስለነዳንና . . . ወዘተ ራሳችንን አተልቀን እናያለን። እኛ ተኮፍሰን እነሱን አኮስሰን እንደምንበልጣቸው እናስባለን። ሃቁ ግን አይደለም። ስለመፀወትናቸውና ትራፊአችንን ስለበሉ ዝቅ አድርገን እናያቸዋለን፣ እንንቃቸዋለን፣ ቦታ አንሰጣቸውም፣ አንሰማቸውም፣ አንገነዘባቸውም፣ አንረዳቸውም . . . ግን ይበልጡናል። በትክክለኛው የሰብአዊነት ሚዛን ዳራቸውም አንደርስ ይልቁናል።

እስቲ ውስጣችንን እንፈትሽ? ልንገዳደራቸው የሚያበቃ ስብእና አለን ይሆን? በእርግጥ አለን ብለን የምናስብ ስንቶቻችን ነን?። በምን መስፈርት?። ራሳችንን በእነርሱ ቦታ እናስቀምጥና እንዳኝ። ያኔ የሰውነት ደረጃና ልካችን ቁልጭ ብሎ ይታየናል። ለኔ የሰብአዊነት ጣርያው፣ ሰው የመሆን ሞገስና ልኩ የልጆቹ ተግባር ነው። የምሬን ነው እንማርበት !።

እዚህ ላይ ከአመት በፊት ይመስለኛል በሸገር ኤፍ ኤም ሬድዮ የሰማሁት መልእክት ትዝ አለኝ - ስርጭቱ በከተማችን ትርፍራፊ (ጉርሻ) ከሚሸጥባባቸው ቦታዎች ከአንዱ ነበር። ተናጋሪዋ ህፃን የዘወትር ተጠቃሚ ነች "እኛ ሁሌም የምንበላው ከናንተ የተረፈውን ነው፣ እባካችሁ እስቲኪኒና ናፕኪን (የእጅ መጠራረግያ ወረቀትና የጥርስ ማጽጃ ስንጥር) አትክተቱበት ይወጋናል፣ ያደማናል . . . አደራ" በማለት ያቀረበችው ተማጽኖ ትዝ ይለኛል። በእውነት ካስተዋልነው ልብ ይነካል - ሌላው ቢቀር፤ አናድርገው።

ምንጭ ፡ የጓደኛየ ገጠመኝ – እውነተኛ ታሪክ
መስከረም 2008 ዓ.ም. አዲስ አበባ
ብሥራት ጴጥሮስ ዮሣ





## የሃሳብ ደዌ

ፉአድና ጓደኛው ፀሀይዋ በከረረችበት ሰአት ጭው ያለውን በረሃማ ምድር አቋርጠው ይጓዙ ነበር። ረጅሙ መንገድ አድክሟቸዋል፣ በቀስታ እየተራመዱ ወደ መሃል ሲጠጉ ድንገት በስተቀኝ መሬቱ ላይ የሁለቱንም ትኩረት የሳበ አንድ ጥቁር ነገር አዩ። ይሁን እንጂ የሚሽከረከረው አውሎ ነፋስ አሸዋውን ሽቅብ እያነነ ጥቁሩን ነገር አንዴ ደበቅ፣ አንዴ ደግሞ ገለጽ በማድረግ ለመለየት አስቸገራቸው።

ፉአድ ወደ ጓደኛው ዞሮ "ይታይሃል? ምን ይሆናል ብለህ ታስባለህ?" አለው።

ጓደኛውም "ጥቁር ፍየል ነው" በማለት መለሰለት። ፉአድ "አ ው! . . . እኔ ግን ቁራ ይመስለኛል" ሲለው ጓደኛው ቆጣ ብሎ "ነገርኩህ እኮ - ጥቁር ፍየል ነው" በማለት ደገመለት።

ፉአድ "እሺ! ቀረብ ብለን እንየውና እናረጋግጥ" በማለት ወደሚታያቸው ነገር ተጠጉ። እየቀረቡት ሲሄዱ ይበልጥ ግልጽ እየሆነ መጣ . . . አሁን በደንብ ይታያል - ቁራ ነው። ፉአድ "ወንድሜ ሥለ አላህ ብለህ? ይህ እኮ ቁራ ነው" አለው። ጓደኛው ግን ራሱን በተቃውሞ በመነቅነቅ "አይደለም ፍየል ነው!" በማለት መለሰለት።

ፉአድ ግራ ገብቶት ዝም እንዳለ፣ ተያይዘው ወደ ቁራው ተራመዱ። አመጣጣቸውን የተጠራጠረው ቁራ ጥቂት አፈገፈገና ተነስቶ በረረ . . . ፉአድ ጮኸ "አላሁ አክበር! እየው ቁራ ነው! ቁራ ነበር ስለሆነም በረረ!" በማለት ድምጹን ከፍ አድርጎ ተናገረ።

ጓደኛው ግን ጮክ ብሎ "ፍየል ነው። ቢበርም እንኳን ጥቁር ፍየል ነው!" አለው ይባላል። ካፈርኩ አይመልሰኝ ማለት ይኸው ነው። ታሪኩን ከዶ/ር መሃመድ ስብስብ ውስጥ ያገኘሁት ቢሆንም ያነሳሁበት ምክንያት አለኝ።

ጉድ ነው፤ እንደዚህ አይነቱን ባህሪይ ምን ትሉታላችሁ? ሁሌም ተቃራኒ። ምንም ያህል ይማሩ ወይም ጭራሽ ማይም፣ በልዩ ልዩ ስኬቶች ይታጠሩ አልያም ምንም ያልሆነላቸው . . . እንደው በተቃርኖ ግትር ደዌ የሚጠቁ በርካታ ሰዎች አሉ። እርግጠኛ ነኝ እስከዛሬ ቢያንስ ሁለት፣ ሶስቱ አጋጥመዋችሁ ሳትታዘቧቸው አይቀርም፣ አይናቸው እያየ እንደ ፉአድ ጓደኛ "በቃ ቢበርም ፍየል ነው" የሚሉ፣ የባሰም አለ።

ሁላችንም በመሰለን ነገር ላይ ጠበቅ አድርገን መከራከር ይቀናናል። የመጀመርያውን ማስረጃ ስናገኝ ግን በማመን እንመለሳለን አልያም በተጠናከረ ሁኔታ አእምሯችን እስኪቀበለው በመከራከር ወይም በማረጋገጥ ሂደት ውስጥ እንቆይና እንቀበለዋለን። እስከዚህ ድረስ ያለው ጤናማው አይነት ሲሆን እየባሰ ሄዶ እንደ ፉአድ ጓደኛ ሲያደርግ ግን አበቃለት የማይድን ካንሰር ሆነ ማለት ነው። እንደው ሳስበው የእድገት ደረጃና መጠን ያለው ይመስለኛል፣ ከዝቅተኛ ወደ መካከለኛ በኋላም ወደ ከፍተኛ ደረጃ እያደገ የሚሄድ፣ በእዚህም አለ በእዚያ ምንጩ እውሸት ነው። መዋሸትን በእንጭጭነቱ ካልገቱት እንደ ክፉ ደዌ ነው፣ እያደር ሲበለጽግ ከሃሰት ጋር ቅልጥ ያለ ፍቅር ውስጥ ይገባና እውነትን ድንገት እንኳ ላለማግኘት ሲሸሻት ይኖራል። በጊዜ ሂደት ጎልብቶ ፍጥጥ ያለው ድርቅና ላይ ሲደርስ ደግሞ እንደ ፉአድ ጓደኛ ያደርጋል። ብቻ እንደዚህ ከመሆንስ ይሰውረን !።

ምንጭ ፡ “Enjoy Your Life” - Moral Stories Collection
*Compiled by Dr. Muhammad 'Abd Al-Rahman Al-'Arifi*
“IT IS NOT IMPORTANT TO ALWAYS BE SUCCESSFUL”
ጥቅምት - 2009 (ዓ.ም.) * አዲስ አበባ

## ትሩፋት

በወፍራም ገመድ አንገቱ ላይ ተንጠልጥሎ ደረቱን የተደገፈው ትልቅ ቅርጫት በተለያዩ ሸቀጦች ተሞልቷል። በመንደሩ ጎዳናዎች ቤት ለቤት እየተዘዋወረ እነዚህን እቃዎች በመሸጥ የሚተዳደረውና ከዛችው ላይ ቆጥቦ የትምህርት ቤት ክፍያውን በመሸፈን ጠንክሮ የሚማረው ምስኪን (ሱቅ በደረቴ) ወጣት ሆዋርድ ኬሊ የተለመደ ተግባሩን እየከወነ ነበር። ሰሞኑን አልቀናውም፣ ገበያው ተዳክሟል። ዛሬ ደግሞ የባሰበት ነው፣ ምንም አልሸጠም። ጠራራዋ ፀሃይ አናት - አናቱን እየወቀረችው፣ ቢጋለው የድንጋይ ንጣፍ መንገድ ላይ ብዙ ተመላልሶ ድክም ብሎታል። እህል ሳይቀምስ ውሎ ያደረ ባዶ ሆዱ ምግብ ቢያሰኘውም በኪሱ በቂ ሳንቲሞች ስላልነበረው የሚበላ ለመለመን ወሰነና ፊት ለፊት ወደሚታየው ቤት አመራ።

በሩን ከፍታ ብቅ ያለችውን እጅግ የምታምር ውብ ልጃገረድ ሲያይ ትንፋሹ ቁርጥ - ቁርጥ አለበት። ምግብ የመለመኑን ነገር ዘንግቶ እየተንተባተበ የሚጠጣ ውሃ ጠየቀ። ድክም ያለ ቁመናውን ያስተዋለችው ልጅ ግን በትልቅ ብርጭቆ የተሞላ ወተት አመጣችለት። ቀዝቃዛውን ወተት ቀስ ብሎ እያጣጣመ ጠጣና እጁን ወደ ኪሱ እየሰደደ "አመሰግናለሁ! ክፍያው ምን ያህል ይሆናል?" በማለት ጠየቃት።

"ምንም መክፈል አይጠበቅብህም" አለችውና አያይዛ "እናታችን በደግነት ለምታደርጉት ተግባር ምንም አይነት ክፍያ እንዳትቀበሉ፤ የሚል ጽኑ መርህ አሳድራብናለች" አለችው። እሱም "እንግዲያው ደግሜ ከልብ አመሰግንሻለሁ" ብሎ ተሰናብቷት ሄደ።

ምስኪኑ ልጅ - ስለደግነት አሰበ፤ ከዚያች ውብ ልጃገረድ የሰማው "በደግነት ከምትፈጽመው ተግባር ምንም ጥቅም አትጠብቅ" የሚለው መርህ ልቡን ነክቶት ቆየ። በዚህም የሰው ልጅ በህይወት ዘመን ቆይታው በየዕለቱ በአካል እያደገና እየተለወጠ እንደሚመጣው ሁሉ አእምሮው በመልካም ትምህርት፣ መንፈሱ በበጎ ምግባር መታነጽ አለበት የሚል ጽኑ እምነት አሳድሮበት ይበልጥ ጠንክሮ በመማርና በመስራት ለትልቅ ደረጃ በቃ።

አመታት አልፈው ከረጅም ጊዜ በኋላ አንዲት በጠና የታመመች ሴት በርቀት ከምትገኝ ትንሽ መንደር ወደ ዋናው ከተማ ትልቅ ሆስፒታል ተላልፋ ትመጣለች። ይህችን ሴት ወደዚህ ሆስፒታል የላካት የክፍለ ሃገሩ ህክምና ማእከል የህመሟን ክብደት ጠቅሶ፣ ከአቅሙ በላይ ስለሆነ በልዩ ከፍተኛ ሆስፒታል እንድትታይ የሚገልጽ ማስረጃ ከዝርዝር የምርመራ ውጤቶቿ ጋር አያይዞ ነበር። ረዳት ሃኪሞቹ ሴትየዋን ከአምቡላንሱ ወደ ህመምተኞች መኝታ በቃሬዛ አጓጉዘው፣ አስፈላጊውን ቅድመ ምርመራ ካጠናቀቁ በኋላ ለዋናው ልዩ ዶክተር ጥሪ አስተላለፉ። መልዕክቱን የተቀበለው ዶክተር ሆዋርድ ኬሊ፣ ህመምተኛዋ የመጣችበትን መንደር ስም ሲሰማ አንዳች አስገራሚ ብርሃን አይኑ ውስጥ ፍንጥቅ አለበት።

ጊዜ ሳያባክን ወደ ጽኑ ህመምተኞች መከታተያ ህንፃ አመራ። ሙሉ ነጭ የህክምና ካፖርቱን ለብሶ የማዳመጫ መሳርያውን አንገቱ ላይ እንዳንጠለጠለ ወደ ክፍሉ የገባው ዶክተር፣ አልጋው ላይ በጀርባዋ - ዟ ብላ የተኛችውን ከሲታ ሴት ፊት ትኩር ብሎ ተመለከተ። የሚያውቀው ፊት፣ ከረጅም ጊዜ በፊት አንድ ቀን ያየው መልክ! አይቶ ያደነቀው ገጽታ፣ መራቡን ሳይነግረው ያወቀለት፣ መጠማቱን ሳያስረዳ የተገነዘበለትና በደግነት የለገሰው ንጹህ ህሊና። አካል ባዳው ያ እጹብ ቁንጅና፣ ደም ግባትና ወዘና ተገፎ፣ በበሽታ ጽኑ ክንድ ክፉኛ ተደቁሷል። በካንሰር ህዋሳት ተሸንፎ አልጋው መሃል ክልትው ብሎ የተጋደመውን ገላ አወቀው። በትክክል የሷ ነው፤ በትክክል እሷ ናት።

በበሳል እውቀቱ አንቱ ከተባሉ ከፍተኛ ሃኪሞች መሃከል አንዱ ለመሆን የበቃው ዶክተር ሆዋርድ ኬሊ፤ ማስረጃዎቿን ይዞ ወደ ቢሮው ተመለሰና ምን ማድረግ እንዳለበት በጥንቃቄ ማሰብ ጀመረ። የሞያ ግዴታውን ጠንቅቆ በመፈፀም ህመምተኞቹን የሚንከባከበው ብርቱ ዶክተር፤ የዚህቹን ምስኪን ሴት ህይወት ለማትረፍ አቅሙ የፈቀደውን ሁሉ ሊያደርግና ሊረዳት ወስኖ ጥረቱን ቀጠለ።

ወራት ከፈጀ ብርቱ ድካምና ያላሰለሰ ክትትል በኋላ በቸሩ አምላክ ፈቃድ የሴትየዋ መዳን ጥሩ ውጤት እያሳየ መጣ። ውሎ ሲያድር ቀስ በቀስ እያገገመች በመጨረሻ ከካንሰር ደዌ ሙሉ ለሙሉ ነፃ ሆና ዳነች። አዲስ ህይወት፣ ዳግም እንደመወለድ የሚቆጠር ነበር። እየተሻላት ከመጣ ወዲህ ግን አንድ ጉዳይ ያሳስባት ጀምሯል፤ ከፍተኛ ወጪ በሚጠይቅ ህክምና ይህን ያህል ረጅም ጊዜ ተኝታ የመረዳቷን ነገር ስታስብ እንዴት ሊሆን እንደቻለ ግራ ግብት ይላታል።

የህመምተኛዋ ደህንነት ከተረጋገጠ በኋላ ከሆስፒታል የምትሰናበትበት ቀን ደረሰ። ዶክተር ኬሊ የሂሳብ ክፍል ኃላፊውን ጠርቶ ጠቅላላ ወጪውን ለማጽደቅ የክፍያ ሰነዱን እንዲያመጣለት አዘዘው። በትእዛዙ መሰረት የክፍያ ሰነዱ ተዘጋጅቶ እንደቀረበለት ዝርዝሩን አነበበውና ከጠረጴዛው መሳብያ ባወጣው የቼክ ጥራዝ ላይ የጠቅላላ ዋጋውን ክፍያ አስፍሮ ሲያበቃ፣ የሠነዱ መጨረሻ ገጽ ላይ ሁለት መስመር ቃላት በመፃፍ ፈረመና ክፍያው ተጠናቆ ሰነዱ ለህመምተኛዋ እንዲሰጣት ላከው።

ህመምተኛዋ የተላከላትን ፖስታ ለመክፈት አልቻለችም - ተጨነቀች፣ በፍርሃት እጇ ተንቀጠቀጠ። ክፍያው እንዲህ ቀላል እንዳልሆነ ታውቃለች። ያለጥርጥር እድሜ ልኳን ስትከፍል የምትኖረው እዳ አልያም ያሏትንና በውርስ ያገኘቻቸውን አሮጌ ንብረቶች እንደሚያሸጣት ገምታለች። እንደምንም ሠነዱን ከፖስታው ውስጥ አውጥታ ማንበብ ጀመረች።

ወረደች . . . ቀጠለች . . . ከዝርዝሩ መጨረሻ ጥግ ላይ የሰፈረ ጽሁፍ አይኗን ሳበው፣ በዝግታ አነበበችው። እንዲህ ይላል . . .

**"በአንድ ብርጭቆ ወተት - ሙሉ ለሙሉ የተከፈለ"**

ዶክተር ሆዋርድ ኬሊ ። *Howard K.*

ከአይኖቿ የፈለቀው የደስታ እንባ ቁልቁል ጉንጯን እያጠበ ሲወርድ፣ የልቧ ምት ስልቱን ቀይሮ በምስጋና ቃና ይረግድ ጀመር። ገርበብ ብለው ከተከደኑት ከንፈሮቿ ስስ ቃላት አፈትልከው ፈሰሱ "አምላኬ ሆይ አመሰግንሃለሁ! ፍቅርህ በመላ የሰው ልጆች እጅ ይድረስ፣ ልባቸውንም ይሙላ። የተሰበረ ህይወትን ለመጠገን ብቸኛው መሳሪያ የልብ ፍቅር ነውና ከአጽናፍ እስከ አጽናፍ ይዳረሰን! - አሜን!" አለች። እኛም . . . አሜን! እንበልና እናብቃ።

የደግነት ውለታን በበጎ ለመመለስ መብቃት በራሱ መታደል ነው።

እውነተኛ ታሪክ ከዶ/ር ሆዋርድ ኬሊ የየቀን ማስታወሻ
ምንጭ፡ (Roger Darlington's World) - “Paid in full with one glass of milk.”

ሰኔ - 2008 ዓ.ም. * አዲስ አበባ



**"የዓለም ለውጥ"**

በየሳምንቱ እሁድ ጠዋት ቤቴ አቅራቢያ በሚገኘው የመናፈሻ ስፍራ ቀላል የሰውነት እንቅስቃሴ ማድረግን ልምዴ ካደረግሁ ብዙ አመታት ተቆጥረዋል። በየጊዜው መናፈሻውን አቋርጬ በስተቀኝ ወደሚገኘው ኩሬ ስራመድ አንዲት ጠና ያለች ሴት ኩሬው ዳር ተቀምጣ አያለሁ። ባየኋት ቁጥር አንድ የብረት ጎጆ የሚመስል ነገር ከአጠገቧ አይጠፋም። ሁሌ ቀረብ ብዬ ምን እንደምትሰራ ለማወቅ

ብጓጓም፤ ባለፈው ሳምንት ጉጉቴ ዳር ደረሰና ልምምዴን ትቼ ወደ ሴትየዋ ሄድኩ። ተጠግቼ ሳስተውል አጠገቧ የነበረው የብረት ጎጆ ሳይሆን በብርማ ብረት እንደመረብ የተሰራ አነስ ያለ ወጥመድ ነበር። ሶስት የባህር ኤሊዎች ውስጡ ወዲያ ወዲህ ይንቀሳቀሳሉ። አራተኛውን ኤሊ ጭኗ ላይ አስቀምጣ በስፖንጅ ብሩሽ በጥንቃቄ ትጠርገዋለች።

"ጤና ይስጥልኝ፣ እንደምን አደርሽ? ዘወትር እሁድ ጠዋት እዚህ ተቀምጠሽ አይሻለሁ፤ በእርግጥ አንቺ ላታስታውሽኝ ትችያለሽ። እኔ ግን ምን እንደምትሰሪ ለማወቅ እፈልግ ነበር፣ እባክሽ ኤሊዎቹን ምን እያደረግሻቸው ነው?" በማለት ጠየኳት።

ፈገግ ብላ "አየህ ማናቸውም አይነት አልጌ፣ ሞራ መሰል ዝልግልግ ቆሻሻና የመሳሰሉት ነገሮች ኤሊዎቹ በአግባቡ እንዳይዋኙና ሰውነታቸው በቂ ሙቀት እንዳያገኝ ከማድረጋቸውም በላይ በጊዜ ብዛት ሽፋናቸውን እየጎዱ ስለሚሄዱ መወገድና መጽዳት አለባቸው" አለችኝ።

እኔም "ዋ ው ው ! በእውነት ይህ አስገራሚ ተግባር ነው" ስል አደነኩላት።

ሴትየዋም አያይዛ "በየሳምንቱ እሁድ ጠዋት እዚህ እየመጣሁ ለሁለት ሰአት ያህል በሃይቁ እየተዝናናሁ የምታያቸውን ልጆች እረዳለሁ፣ ይህ እኔ በግሌ የማደርገው ለውጥን የመፍጠር መርሃ ግብሬ ነው" በማለት አስረዳችኝ።

"ግን እኮ የባህር ኤሊዎች የሕይወት ዘመናቸውን ሁሉ ሽፋናቸው በአልጌና በሃረግ መሰል ልዩ ልዩ የውሃ ውስጥ ተክሎች ሲተበተብና ሲያያዝባቸው እንደሚኖር አልተገነዘብሽም?" ስል ጠየኳት።

"አ ው ! ይሆናል፤ እንደዛ ናቸው" አለችኝ ቀዝቀዝ ብላ።

እራሴን እያከኩ "እሺ - ይሁን ግን፤ ጊዜየን በተሻለ ነገር ላይ እያጠፋሁ ነው ብለሽ ታስቢያለሽ? እኔ እንደማስበው ያንቺ ድካም በአጠቃላይ ትሁትና አዛኝነትሽን የሚያሳይ ነው፣ ሆኖም እጅግ በርካታ የባህር ኤሊዎች በአለም ዙርያ ይኖራሉ። ዘጠና ዘጠኝ በመቶ የሚሆኑት እነዚህ ኤሊዎች ሽፋናቸውን የሚያፀዱላቸው እንደ አንቺ አይነት ቀና ሰዎች የሏቸውም። ድርጊትሽ ከፋት የለውም . . . ነገር ግን ይህ ውስን ልፋትሽ በእውነት የሚያመጣው ለውጥ ይኖራል ብለሽ ታስቢያለሽ?" አልኳት።

ሴትየዋ ከትከት ብላ ሳቀች፤ ቁልቁል ጭኗ ላይ ወዳስቀመጠችው ኤሊ እየተመለከተች፤ ሽፋኑ ላይ የቀረችውን የመጨረሻ አልጌ ጠርጋ አነሳችና . . . ድምጿን ከፍ አድርጋ "የኔ ልጅ . . . የአለማችን ሁሉም ለውጦች አንድ ተብለው የተጀመሩ ናቸው . . .። ይህ የምታየው ወጣት ኤሊ መናገር ቢችል ኖሮ የእኔን የለውጥ ተግባር በሚገባ ባስረዳህ ነበር" አለችኝ።

ለጊዜው ኤሊው አልተናገረም መናገር ቢችል ግን እንዲህ ነበር የሚለው . . . "አንተ ጅል! አንድ ሺህ ኪሎ ሜትር በአንድ እርምጃ ይጀመራል፣ በአለም ላይ ለውጥን ማምጣት ትችላለህ። ልብ በል ሁሉም በአንዴ አይሆንም፣ ነገር ግን አንድ ሰው፣ አንድ እንስሳና አንድ ጥሩ ነገር በአንድ ጊዜ አድርግ እናም ውጤቱን በትእግስት ተከታተል። ዘወትር ጠዋት ከእንቅልፍህ ስትነቃ በእለትህ የምትፈጽመውን በጎ ነገር አስብ፣ ለውጥን ታመጣለህ። ይህ በእውነት ይሰራል!"። እንደሚል ቅንጣት አልጠራጠርም።

ምንጭ ፡ "40 Short Stories that Will Change the Way You Think" በሚል ርእስ በ"ማርክ ቼርኖፍ" ለንባብ ከበቁት አንዱ "All the Difference in the World"

ግንቦት - 2008 ዓ. ም. * አዲስ አበባ

## "ምርጡ ሰው"




እሁድ ከቀትር በኋላ የአገር ውስጥ በረራዋን የጀመረችው የግል አውሮፕላን አንድ ዶክተር፣ አንድ ጠበቃ፣ አንድ ቄስና አንድ ትንሽ ልጅን አሳፍራ ነበር። ያለምንም እንከን መሬት የለቀቀችው አውሮፕላን ለግማሽ ሰዓት ያህል ከበረረች በኋላ ሞተሩ ውስጥ በተፈጠረ እክል በሃይል ተንገጫገጨች። ወዲያው የማስጠንቀቅያ መብራቶቹ ብልጭ ድርግም እያሉ ሁሉም ነገር ወደ አስፈሪነት ተቀየረ። የአውሮፕላኑ አብራሪ በነበረው ከፍተኛ ብቃት አውሮፕላኑ በዝግታ ወደ ቁልቁል መውረድ እንደ ጀመረ ድምጹን ከፍ አድርጎ "ሰዎች አዝናለሁ! ሁኔታዎች ከመበላሸታቸው በፊት በአስቸኳይ ፓራሹቱን እያነሳችሁ እኔ እንደማደርገው አድርጉ" በማለት የአደጋ መውጫውን በር ከፍቶ ተወረወረ። በሚያሳዝን ሁኔታ የቀሩት ሦስት ፓራሹቶች ብቻ ነበሩ።

ዶክተሩ አንዱን ፓራሹት አነሳና "እንደምታውቁት እኔ የሕክምና ዶክተር ነኝ፤ ከተለያዩ በሽታዎች ጋር በመታገል የሰዎችን ህይወት ማዳን ሥራዬ ነው፣ ብዙዎች ይፈልጉኛል ለዚህም መኖር አለብኝ" በማለት እንደ አብራሪው ዘሎ ወረደ።

ጠበቃው ቀጠለና "እኔ ጠበቃ ነኝ፣ ያውም እጅግ ድንቅ የሆነው ሞያ ባለቤት። የአለም ምርጥ ሰዎች ማለት ደግሞ ጠበቆች ነን፤ እናም በማያጠራጥር ሁኔታ እፈለጋለሁ" አለና አንዱን ብድግ አድርጎ ዘለለ።

ቄሱ ወደ ትንሹ ልጅ ተመለከቱ፤ ከዚያም "የኔ ልጅ አንተ ገና ለጋና ወደፊት ብዙ ብዙ ነገሮች የሚጠብቁህ ታዳጊ ነህ፣ እኔ ደግሞ ከእድሜዬ አብዛኛውን አገባድጃለሁ። መኖር ያለብህ አንተ ነህ፣ ይቅናህ፣ እግዚአብሔር ይባርክህ" በማለት ቀሪውን አንድ ፓራሹት ሰጡት።

ልጁ ግን ፓራሹቱን መለሰላቸው። ቄሱ ግራ ተጋብተው ላለመቀበል ወደ ኋላ አፈገፈጉ . . . ። ልጁ ፈገግ እንዳለ "አባቴ አይጨነቁ ምንም ችግር የለም፤ ያ ከአለም ምርጥ ሰዎች አንዱ የሆነው ድንቅ ጠበቃ የኔን ቢጫ ቦርሳ አንጠልጥሎ ነው የወረደው። ስለዚህ ሁለታችንም ፓራሹት አለን" አላቸው። ከዚያም ልጁና ቄሱ ተከታትለው ዘለሉ።

ወዳጆቼ . . . የተሰማራንበት የሥራ መስክ ማንነታችንን አይገልጽም፣ ልንመዘንበትም ሆነ ልንመፃደቅበት አይገባም። ከሁሉም ከሁሉም ሰብአዊነት ይበልጣል . . . እርሱ ነው ምርጡ።

ምንጭ : m www.moralstories.org
ኅዳር - 2009 (ዓ.ም.) - ላንጋኖ




<u>**አይረሴው ልዩ ኦሎምፒክ**</u>

ከአመታት በፊት (እ.አ.አ.) በ 1976 ዋሺንግተን - አሜሪካ ውስጥ ተካሂዶ በነበረው የተለያየ የአካልና የአእምሮ ጉዳት ያለባቸው ሰዎች በሚካፈሉበት ልዩ ኦሎምፒክ (Paralympic Games) ውድድር ወቅት እንዲህ ሆነ። አራት ወንድና አምስት ሴት በጠቅላላ ዘጠኝ የአካልና የአእምሮ ጉዳት ያለባቸው ወጣት አትሌቶች የ 100 ያርድ ወይም የ 90 ሜትሩን ሩጫ ለመወዳደር ተዘጋጅተው ይጠባበቃሉ።

የማስጀመሪያው ምልክት ተተኮሰ፣ ሁሉም ሩጫቸውን ቀጠሉ። የአሸናፊነትን ክብር ለመቀዳጀት፣ ቢቻል ወርቁን ለማግኘት፣ ካልሆነም በደረጃ ሰንጠረዥ ብርና ነሃሱን አልመው ተንደረደሩ። በዚህ መሃከል በግምት 45 ሜትር ያህል እንደሮጡ፤ ሰባት ቁጥር የተፃፈበትን ሰማያዊ መለያ ለብሶ በአራተኛው መስመር ላይ ይሮጥ የነበረው ተወዳዳሪ አደናቅፎት ወደቀ። እንደምንም ተነስቶ ለመሮጥ ሲሞክር በድጋሚ ወደቀና የመሮጫ ሜዳው ላይ በደረቱ እንደተኛ በእልህ ያለቅስ ጀመር።

መሪር ለቅሶውን የሰሙ ስምንቱም ተወዳዳሪዎች ፍጥነታቸውን ቀንሰው ወደ ኋላ ተመለከቱ። አንድ በአንድ አቅጣጫቸውን ቀይረው ወደ መጡበት ተመለሱና ሜዳው ላይ ተዘርሮ የሚያነባውን ልጅ ቁልቁል እያስተዋሉት ቆሙ።

ወዲያው ቁጥር ስምንት አካል ጉዳተኛዋ አትሌት ጎንበስ ብላ ጉንጩን ሳመችውና "ይህ የበለጠ ብርታትና ጥንካሬን ይሰጥሃል" በማለት በመዳፏ እንባውን እየጠረገች፣ እቅፍ አድርጋ አነሳችው። ሁሉም እርስ በእርስ እጆቻቸውን እንደሰንሰለት አቆላልፈው ወደ ውድድሩ መጨረሻ መሮጣቸውን ቀጠሉ። እጅ ለእጅ የተያያዙት አትሌቶች የፍፃሜውን መስመር አልፈው የአሸናፊነት ገመዷን በጋራ በጥሰው ሲገቡ ገፆቻቸው ላይ የሚነበበውን የጽናትና የድል አድራጊነት መንፈስ ሊገልጽ የሚችል ምንም አይነት ቃል አልነበረም።

እስታዲየሙን የሞላው ተመልካች ከመቀመጫው ተነስቶ ለደቂቃዎች በዘለቀ ጩኸትና ጭብጨባ አካባቢውን አናጋው። ከህዝቡ መሃል አንዳንዶቹ ከፍ ባለ ድምጽ "እናንተስ አካል ጉዳተኞች አይደላችሁም! ትልቅ ነገር አሳያችሁን፤ ጉዳተኞች አይደላችሁም! ከማንም የተሻላችሁ ናችሁ . . . እያሉ ይጮሁ ነበር። ይህ በስፍራው የነበሩም ያልነበሩም የአካባቢው ሰዎች በተለያየ አጋጣሚ እያነሱ እስከ ዛሬ ድረስ የሚያወሩት ታሪክ ነው። እውነትም፤ እነዚህን ነው ጉዳተኞች የምንላቸው?።

ውድድሩ የተለያየ የአካልና የአእምሮ ጉዳት ያለባቸውን ብቻ የሚያካትት ነበር፣ ተወዳዳሪዎቹም እንደዛው። ድርጊታቸውን ስናይ ግን ውድድርንና ማሸነፍን ከህይወት አንፃር በማስተዋል ረገድ "ሙሉ አካልና ያልተሰናከለ አእምሮ አለን" በሚል ቀቢፀ ጤና ከምንኮራው ከእያንዳንዳችን የላቀና እጅግ የረቀቀ ስለመሆኑ መመስከር ግድ ይለናል።

የሕይወት እርካታ ሌሎችን መደገፍና አሸናፊ እንዲሆኑ ማገዝ ማለት ነው። የሕይወትን ጎርበጥባጣ መንገድ በአሸናፊነት መዝለቅ ትርጉሙ ሌሎች ምንም ያህል ቢዘገዩ፣ ወደ ኋላ ቢያስቀሩን፣ ችግሮችን መቋቋምም ሆነ መሰናክሉን መሻገር ቢያቅታቸው . . . በመቅረብ፣ በመርዳት፣ በመደገፍና አስፈላጊውን ሁሉ በመለገስ ከጎናቸው መቆምና በአሸናፊነት እንዲዘልቁ ማድረግ ነው። በጋራ ማሸነፍ! . . . ሌሎችን ሳያበላልጡ እኩል መውደድ ማለት ነው። የአሸናፊዎች አሸናፊነት ክቡር ድልም የዘጠኙ ጉዳተኛ አትሌቶች አይነት ጣፋጭ ድል ነው።

ይህ "Crossing the Finish Line Together" በሚል ርእስ ሲያትል ውስጥ የተፈፀመ እውነተኛ ታሪክ እንደሆነ ተጠቅሶ በተለያዩ ማሕበራዊ ድረ ገጾች ላይ የሰፈረ ሲሆን፤ ስለእውነተኛነቱ ባደረኩት ማጣርያ ከፊሉ ብቻ በእውነት የተፈፀመ ታሪክን ተንተርሶ የተፃፈ መሆኑን ማረጋገጥ ችያለሁ። አንዳንድ ታሪኮች መሳጭነታቸው እንዲጎላ በዚህ አይነት መቅረባቸው የተለመደ መሆኑ፤ ከማስተማራቸው አንፃር ክፋቱ እምብዛም አይታየኝም።

ምንጭ፡ www.Snopes.com
በእውነተኛ ታሪክ ላይ የተመሰረተ ቦታው Spokane, Washington, USA
ጊዜው - (እ.አ.አ.) 1976



## "የአዕምሮ ሞገስ"

በሆስፒታሉ ህንፃ ሁለተኛ ፎቅ፣ ልዩ እንክብካቤን የሚሹ ህመምተኞች ክፍል በሩ በትንሹ ተከፍቷል። ነጩን ስስ መጋረጃ ያለ ገደብ ተሻግራ ግድግዳው ላይ የምትነጥረው የመስከረም ፀሃይ፤ ክፍሉን በሚያነቃቃ ብርሃን ብትሞላውም ጥግ ባለው አልጋ ላይ የነበረው ድባብ ግን ፍጹም ተቃራኒ ነው።

ሰውነታቸው ድቅቅ ያለና ክሳታቸውን ለመግለጽ የሚያስቸግር፣ በጡረታ ላይ የሚገኙ አዛውንት ወታደር፤ ዙሪያው ብልጭ ድርግም በሚል ኤሌክትሮኒክስ በታጠረው አልጋ ላይ ተኝተዋል። አፍንጫቸው ላይ የተሰኩት አየር መስጫና ልዩ ልዩ መርጃ መሳሪያዎች፣ ሰውየው ያሉበትን አስጊ ሁኔታ ይጠቁማሉ። ነርሷ በልብ ድካም የሚሰቃዩትን ህመምተኛ አስተካክላ ለማስተኛት ትታገላለች። ሙሉ ወታደራዊ የደንብ ልብስ የለበሰ ባለ ማእረግ የባህር ኃይል መኮንን፣ ገርበብ ያለውን በር ከፍቶ ገባ። ቀና ብላ እንዳየችው "አባባ - አባባ - ይኸው ልጅዎ መጣ" አለቻቸውና ወደ አልጋው ጠራችው። ይህንን ቃል ብዙ ጊዜ ደጋግማዋለች፣ ሰውየው ቀን ከሌት የብቸኛ ልጃቸውን ሥም ይጠሩና ለግላጋውን የጦር መኮንን ዓይኑን ሳያዩት እንዳይሞቱ ይፀልዩ ስለነበር ራሳቸውን በሳቱ ጊዜ ይነቁ ዘንድ ልጅዎ መጣ! ልጅዎ መጣ! እያለች ትጠራቸዋለች። አሁን ግን የምሯን አለችው።

ምስኪኑ አዛውንት አይናቸው ተርገበገበና በዝግታ ተከፈተ፤ በጭጋግ ውስጥ ነፋስ እንደሚወዘውዘው ዝግባ፣ የባህር ኃይሉን ፀአዳ የደንብ ልብስ ዝቅ አድርጎ የለበሰ ወጣት፣ ከአልጋው ትይዩ ቆሟል፣ ትኩር ብለው አዩትና በስንት ድካም ተንጠራርተው እጃቸውን ዘረጉለት። ለመንካት የሚያስፈራና ስጋ የፈጠረበት የማይመስለውን እጅግ የሰለለ እጅ ወጣቱ መኮንን ጎንበስ ብሎ በመዳፎቹ መሃከል ያዘውና አይበሉባቸውንና ቀጫጭን ጣቶቻቸውን በስስት ያሻሻቸው ጀመር። የአዛውንቱ ፊት በዝግታ እየፈካ ሲሄድ፣ ከወራት በኋላ ውሃ ጥማቱን የተወጣ የቆላ መሬት ይመስል ነበር። ደርቀው ኩበት በመሰሉት ከንፈሮቻቸው ጥቂት ቃላት አነበነቡ፤ ለማዳመጥ ተጠጋቸው ነገር ግን "ልጄ" ከምትለው ቃል በስተቀር ሌላ ምንም መስማት አልቻለም። የፊታቸው ወዝና እየፈካ የመጣው ገፃቸው፤ የእርካታቸው ምልክት ለመሆኑ አያጠራጥርም። በቀኝ ጣቶቹ ፊታቸውንና ፀጉር የሸሸው ራሳቸውን እየዳበሰ በቀስታ "አባባ . . . አይዞህ - አይዞህ . . . አባባ!" አላቸው፤ ጥብቅ አድርገው ያዙት፤ እሱም በአፀፋው ጨበጥ አደረጋቸው። ያኔ በደም ሥሮቻቸው ውስጥ እንደ ኤሌክትሪክ ሞገድ ያለ ለመግለጽ የሚከብድ ሃይል ሲሰራጭ ታወቀው።

ነርሷ ወንበር አመጣችለትና እንዲቀመመጥ በምልክት ነገረችው። ቁጭ አለ . . . ፀሃይ ጠልቃ ምሽቱ እየነገሰ ሲመጣም ወጣቱ የባህር ኃይል መኮንን ከነበረበት አልተንቀሳቀሰም። ከሞት ጋር ትግል የገጠሙት ሽማግሌ፣ አልፎ አልፎ እንደ መበርገግ እያሉ እጁን ያዝ ያደርጉታል፤ እሱም እየደባበሰ በመልካም ቃላት ያበረታታቸዋል። መሽ። ነርሷ ተመልሳ ስትመጣ እዚያው ስላየችው ተገርማ፤ "እባክህ ሄደህ አረፍ በል - በዚህ አይነት ከቆየህ ነገ ቆመህ መሄድ አትችልም" አለችው፤ እሱ ግን ፈገግ ብሎ ራሱን በመነቅነቅ እሽታውን ገልጾላት ዝም አለ።

የማታው ትእይንት ለየት ያለና የሚያስቸግር አይነት ሆነ፣ የህመምተኞቹ ቁጥር ብቻ ሳይሆን ግርግሩና ጫጫታውም ጨምሮ ነበር። የኦክስጂን በርሜሎች ኳኳታ፣ ህመም የጠናባቸው በሽተኞች ማቃሰት፣ የጣር ድምጽና ስቅታ . . . ከአስታማሚ ቤተሰቦች ለቅሶ ጋር ሲደመር፤ ስፍራው ፍጹም ምቾት ይነሳል። ሥራቸውን አጠናቀው የሚወጡትና ሥራ የሚጀምሩ የማታ ተረኛ ሃኪሞች ድምፃቸውን ሳይቀንሱ፤ ሰላምታና የመልካም ምኞት መግለጫዎችን ይለዋወጣሉ። ሁካታ ባየለበት ክፍል፣ በደብዛዛው የምሽት ብርሃን ውስጥ ወጣቱ መኮንን፤ የሽማግሌውን እጅ እንደያዘ ተቀምጧል።

ነርሷ ለመጨረሻ ጊዜ መጣች፤ የሽማግሌው ጉጉትና የልጁ ጥንካሬ ስለከነከናት ጥቂት አርፍዳለች። ወደ ጆሯቸው ጠጋ ብላ ጠራቻቸው፤ "አባባ - አባባ" ከንፈራቸው ይንቀሳቀሳል፤ የሚሉት ግን አይሰማም። አሁንም በድጋሚ እረፍት እንዲያደርግ አስታውሳ ተሰናብታው ወጣች። አዛውንቱ ፈገግ ለማለት ሞከሩ፤ ልጃቸውን አጥብቀው የያዙበት መዳፋቸው ግን እየላላ መጣ። ጥቂት ቆይቶ ሽብረክ አለና አልጋ ልብሱ ላይ አረፈ ። ወጣቱ የባህር ኃይል መኮንን ህይወት አልባውን እጅ ከዚህ በላይ ይዞ መቆየት አላስፈለገውም። በዝግታ አስቀምጦት ነርሷን ለመጥራት እየሮጠ ተከተላት። ሽማግሌው እስከወዲያኛው አሸልበዋል። ነርሷና የክፍሉ ሰራተኞች ተጋግዘው አስፈላጊውን ሁሉ ካመቻቹ በኋላ የሽማግሌውን አስከሬን በተሽከርካሪ ቃሬዛ ይዘውት ወጡ።

ነርሷ መለስ አለችና ፊት ለፊት ወደቆመው ልጃቸው በመጠጋት፤ "በጣም አዝናለሁ! መቼም አመጣጥህ ተዓምር ነው! እንደዛ ናፍቀውህ ሳያዩህ ቢሞቱ ኖሮ ትልቅ ፀፀት ነበር፤ እ . . ."

ወጣቱ የባህር ኃይል አቋረጣትና፤ "ለመሆኑ እኚህ ሰው ማን ነበሩ?" በማለት ጠየቃት።

ነርሷም - "እሳቸውማ አባትህ ነበሩ፤ አይደሉም እንዴ?" መልሳ ጠየቀችው፤ ግራ በመጋባት።

"በፍጹም! ከዛሬ በፊት በሕይወቴ አይቻቸው አላውቅም፤ የጠራሽኝ አንቺ ነሽ!" አላት፤ አፍጥጦ እያያት፡፡

"አዎን! የባህር ኃይል መኮንን የሆነ ልጃቸውን ይመጣል ብለው በጉጉት ይጠብቁ ስለነበር፣ አንተ መስለኸኝ ጠራውህ። ታዲያ አንተስ ምንም ሳትል የያዝካቸው ለምንድነው?" ጠየቀችው።

"እኔ ስህተት እንደተፈጠረ ያወቅሁት ወዲያው ነበር፤ ቢሆንም ልጃቸውን በብርቱ የሚፈልጉ መሆናቸውን ስለተረዳሁ ሁሉንም ነገር ትቼ ያዝኳቸው። ሌላ ምን ማድረግ እችል ነበር? የሚናፍቁት ልጃቸው አጠገባቸው አልተገኘም፤ ያለሁት እኔ ነኝ። የደንብ ልብሱን ሲያስተውሉ የተብረከረከ ሰውነታቸው ሌላ የምችለው ምንም አይነት ነገር ቢኖር ከማድረግ አይገድበኝም ነበር። በዚያን ሰአት ልጃቸው አለመሆኔን ለሳቸው ቀርቶ ለማንም ከማስረዳት በቀጥታ ማድረግ ያለብኝን ብቻ አደረግሁ። እስቲ አስቢው ብናገር ምን ይጠቅማል?" አላት።

"በጣም አዝናለሁ - አልተቀበልከም እንጂ እኔ እንድታርፍ ደጋግሜ ነግሬህ ነበር" አለችው።

"የኔ እህት ልልሽ የምችለው ነገር፤ ምን ያህል እንደሚፈልጉኝ ተረዳሁ እናም ቆየሁ . . . እስከመጨረሻው መጠበቅም ነበረብኝ፤ በትእግስት ጠበቅሁ - ሁሉም የፍቅር ጉዳይ ነው!" ብሏት ወጥቶ ሄደ።

ወጣቱ የባህር ሃይል መኮንን ደረጃውን በመውረድ የሆስፒታሉን ግቢ ለቆ እስኪወጣ ድረስ ነርሷ፣ ህመምተኞችና በክፍሉ ውስጥ የነበሩ ሁሉ በዓይናቸው ሸኙት። ሰብአዊ ድርጊቱ ግን በመልካም ተምሳሌትነቱ ከአእምሯቸው መቼም አይጠፋምና . . . ለትውልድ ሲተርኩት ይኖራሉ። ስለ ፍቅር ነውና። ይህንን መሰል ነገሮች አንዳንዴ ሊገጥሙን ይችላሉ። ተናግረን ወይም አድርገን አፀፋው ሌሎችን ሊጎዳ ቀርቶ እንደማይጠቅም ከተረዳን መተውን የመሰለ ነገር የለም። ፀፀቱም አይጣል ነው። እንደ ወጣቱ የባህር ሃይል መኮንን በበጎ መመለስ ደግሞ ከመታደልም በላይ መመረጥ ነው . . . የአእምሮ ሞገስ።

ምንጭ : Roger Darlington World - thoughtful stories, motivational tales, and pieces of wisdom from around the world. Title: “Love stays”

የካቲት 2009 * አዲስ አበባ

**“The key to the future of the world is finding the optimistic stories and letting them be known.”**

American singer, songwriter - Pete Seeger (1919-2014)

## እይታና እውነታ



ርእሳችን "እይታና እውነታ" የሚል ነው። ወይም "እውነትን እውነት የምንለው በተገነዘብነው (በተረዳነው) ልክ ነው" ማለት ይቻላል። "Truth is a matter of Perception" እስቲ ይህ ጉዳይ በግብረገባዊ ተረት ሲገለጽ ምን እንደሚመስል ለማየት እንሞክር . . . ነገሩ እንደዚህ ነው።

አምስት አይነ ስውራን ጓደኞሞች ናቸው። ከእለታት በአንዱ ቀን ከመንገድ ወጣ ብለው ሲጓዙ አንድ ዝሆን ያገኛሉ፡፡ እናም እያንዳንዳቸው የገጠማቸውን ነገር በመዳሰስ ስለ ምንነቱ እርስ በእርስ መገላለጽ ጀመሩ። የመጀመሪያው ዓይነ ስውር የቆመው ከዝሆኑ ፊት ለፊት ስለነበር ኩንቢውን በጥንቃቄ ዳበስ - ዳበስ አድርጎ፤ "ወዳጆቼ! ይህ ትልቅ የፕላስቲክ ቱቦ ነው" አላቸው።

ሁለተኛው ዓይነ ስውር ከዝሆኑ በስተኋላ ስለነበር፣ ጭራውን ከላይ እስከ ታች በመፈተሽ ድምጹን ከፍ አድርጎ "መጥረጊያ ነው፤ ያውም ባለ ረጅም ዘንግ ጣርያና ኮርኒሶችን ለማጽዳት የሚያገለግል መጥረጊያ!" በማለት በኩራት ተናገረ፡፡

ሦስተኛው ዓይነ ስውር ደግሞ ከዝሆኑ ጎን በስተግራ በኩል ተንጠራርቶም ቢርቅበት መሰላል ላይ ሆኖ "ወንድሞቼ፤ ነገርየው በቆዳ የተለበጠ ትልቅ ግድግዳ ነው፤ ይኸው ተደፍፌው አረጋግጫለሁ" በማለት ገለፀላቸው።

አራተኛው ጓደኛቸው ለዝሆኑ ጆሮ ቅርብ ነበርና የዝሆኑን ትልቅ ጆሮ አሸት - አሸት አድርጎ፤ የጀልባ ተራዳ መሆኑን አመነ፣ ወዲያው ጮክ ብሎ "ጓዶቼ . . . ሶስታችሁም ልክ አይደላችሁም! ይህ ያገኘነው ነገር ጀልባዎች በንፋስ ኃይል ተገፍተው እንዲሄዱ የሚያግዛቸው ለስላሳ ሸራ ነው" አላቸው።

በመጨረሻም ከዝሆኑ የፊት እግር አጠገብ ቆሞ በትዝብት ሲያዳምጥ የነበረው አምስተኛው ሰው የዝሆኑን እግር እየዳበሰ "ሁላችሁንም ታዘብኳችሁ፤ ይህ ነገር እናንተ እንዳላችሁት ሳይሆን፤ የትልቅ ዛፍ ግንድ ነው" በማለት ጨዋታቸውን ደመደመው።

በዚህ አይነት የግንዛቤ ደረጃ ሁሉም የመሰላቸውንና የተረዱትን በማብራራት አልተወሰኑም፡፡ እንዲያውም የራሳቸውን ግምት ብቻ ሙሉ ለሙሉ በማመን የሌሎቹን ውድቅ አደረጉ። አንደኛው የሁለተኛውን አይነ ስውር ሃሳብ ሲሰማ "ምን አይነት ድንጋይ እራስ ነው! ቱቦና መጥረግያን ምን አመሳሰላቸው!" ሲል የቀሩትም እንዲህና እንዲህ እያሉ ከራሳቸው በስተቀር የሌሎቹን ግንዛቤ እንደ ስህተት ቆጥረው፣ አንዱ የሌላውን ሃሳብ ሲያጣጥል ጀንበሪቷ ጠለቀች። ስለዚህ አንዱ ነገር በአምስቱም ዘንድ ተሸንሸኖ የተለያየ ክስተት ሆነባቸው። በጉዳዩ ላይ የጋራ የሆነ ምስል እስካልቀረጹ ወይም የጋራ ግንዛቤ ላይ እስካልደረሱ ድረስ እንቆቅልሽነቱ ቀጣይ ይሆናል።

ከዚህ ታሪክ ጋር ተያያዥ የሆነ የግል ገጠመኜን ላውጋችሁ። ከዛሬ ሠላሳ አመት በፊት ነው (በ1979 ዓ. ም. መጨረሻ ግድም) ቦታው በወቅቱ አጠራር ከፋ ክፍለ ሃገር፣ ከፋ አውራጃ ከቦንጋ ከተማ በሸሽንዳ በኩል ወደ ቴፒ በሚወስደው መንገድ ትንሹ ጌሻ ወረዳ ውስጥ የሰፈራ መንደሮችን በማስተባበር ሥራ ላይ ተመድቤ፤ በገጠሩና አካባቢው ሥፍራዎች እንቀሳቀሳለሁ። በዚያ እድሜዬ ስለ ዝሆን አንዳችም ግንዛቤ አልነበረኝም፤ በአንድ ወቅት ከቢጣ ከተማ ተነስተን አላሞ በረሃን በማቋረጥ ኦዳ ሰፈራ ጣብያን እንጎበኝና መዳረሻችን ቴፒ ከተማ ነበር። ከሰአት በኋላ በግምት አስር ሰአት ገደማ ይሆናል፣ ቁልቁል አላሞን በመውረድ ላይ ሳለን (ነብሱን ይማረውና) ዝሆን አይቼ እንደማላውቅ ያጫወትኩት የመስክ ጓደኛዬ "ያውልህ ዝሆን!" ብሎ አባነነኝ። ማመን አልቻልኩም፤ መኪናችን ከመንገዱ ዳር እንደቆመች በስተግራ ወደ ሰንበሌጡ ሜዳ አፈጠጥኩኝ ፣ . . . ሆኖም ጭስ ከጠገቡ አምስት ያህል ጎጆ ቤቶች በስተቀር ምንም አልታየኝምና "የታሉ?" አልኩት "እኛውልህ" እያለ ወደ ፊት ለፊታችን ይጠቁመኛል "ምኑ ጋ? ከጎጆዎቹ በየት በኩል?" እያልኩ ሳጣድፈው እንደመሳቅ አለና "እዚህ ዱር መሃል የምን ጎጆ አመጣህ? ዝሆኖች ናቸው" ብሎኝ አረፈ፡፡ እናም በደመነፍስ ራመድ! ራመድ! እንደማለት ቀረብኳቸው . . . በዓይኔ በብረቱ ተጠግቼ አየኋቸው፤ ጓደኛዬ ልክ ነው። (በዚያች ቅጽበት የተሰማኝ ደስታ) "ጢስ የጠገቡ ጎጆ ቤቶች" የመሰሉኝ ያለጥርጥር አምስት ዝሆኖች ነበሩ፤ አዎ ምንጊዜም እውነታ ከእይታ ጋር እጅጉን የተቆራኘ መሆኑን ከዚህ ግለ-ገጠመኝ ማረጋገጥ ይቻላል።

ከላይ በተዋወቅናቸው አይነ ስውራን ጓደኞሞች መካከል የነበረው እሳቤና ግንዛቤ ለየቅል ሆነና ሁሉም የየራሳቸውን አረዳድ እንደ ፍጹም እውነታ ወስደው ደመደሙት። ይህ ብቻም ሳይሆን አንዱ የሌላውን አመለካከት "የእብድ ጨኸት" አደረገው። በመሰረቱ የአይነ ስውራኑ ስህተት የመረዳት ችግር ወይም የላቀ እውቀትን ግድ የሚል ውስብስብ ጉዳይ አይደለም። የእነርሱ አብይ ችግር የቆሙበትን ቦታ አለመቀየር ነው። አንዳቸውም ቢሆኑ እርስ በእርስ ቦታቸውን (የቆሙበትን ሥፍራ) ለመለዋወጥ አልጠየቁም፣ እኔ ከዚህ ሆኜ ይህንን ከተረዳሁ ለምን ከዚያ ሆኜ አላየውም አላሉም። በሌላ በኩል ደግሞ ማናቸውም የሌላኛቸውን ሃሳብና አመለካከት ለመረዳት አልሞከሩም። በአጠቃላይ ሁሉም ይበልጥ ጠምዛዛና የማይበገሩ መሆናቸውን ለማስመስከር፣ በየራሳቸው የአመለካከት ኩሬ ውስጥ ሰምጠው ሌሎችን ያጣጥላሉ፡፡ አልፈው ተርፈው ራሳቸውን የእውነት ደቀ መዝሙር አድርገው እስከመቁጠር ይደርሳሉ።

አምስቱ ጓደኞሞች ዝሆንን በዓይናቸው አይተው ላያውቁ ይችላሉ፤ ነገር ግን የእያንዳንዳቸውን አመለካከትና ግንዛቤ ተደማምጠው በእኩል ደረጃ ቢቀበሉትና ገጣጥመው ሊያነቡት ቢሞክሩ፤ እንዲሁም ቦታቸውን ተቀያይረው አንዱ ያየበትን አቅጣጫና የአስተሳሰብ አድማስ ሌላው በቅንነት ቢያገናዘብ፤ ላቅ ሲል የአምስቱም ጓደኞሞች ጥምር እውቀት የተሻለና ለእውነታው እጅግ የቀረበ ምስል መቅረጽ በቻለ ነበር። ልብ በሉልኝ! እኛ በማናውቀው ነገር ላይ ከእነርሱ የባስን ነን። ወደ ዋናው ቁም ነገር ተመልሰን ጠቋሚ ጣታችንን ወደራሳችን ብናመለከት፣ ከቶ እኛስ ምን እንመስል ይሆን?። አዎ! የዚህ አጭር ታሪክ መሰረታዊ አላማም ይኸው ነው፤ ከልብ አለመደማመጥ፣ እኔን ብቻ ስሙኝ፣ የእኔ ብቻ ትክክል ነው እና የሌሎችን ሃሳብ ማጣጣል . . . ወዘተ የአስተሳሰብ ነቀርሳዎች እንደ መዥገር ተጣብቀውብናል። ከእነርሱ የጎደለ ከእኛም ስለመጉደሉ የማይጠረጠር፣ በሁላችንም ዘንድ የሚፈለግ ዋናው የችግራችን መንስኤ፣ የሌሎችን ሃሳብ አለመቀበል ነው (ደምቆ - ይሰመርበት)።

እኛ ብርሃንና ጨለማን ስለለየን ወይም ማየት የሚቻለንን ብቻ በማየታችን ዓይናማ ነን ማለት አንችልም። ማየት ከእዚህኛውም ሆነ ከእዚያኛው ፍጹም የላቀ ነው። ማስተዋል፣ ማወቅ፣ መረዳት፣ በጥልቀት መገንዘብ . . . ወዘተ። ከዚህ ውጪ ያለው ማፍጠጥ ከማየት አይመደብም። አብዛኞቻችን አለምን የምናየው ከራሳችን አመለካከት አንፃር ብቻ ነው። መረዳት የምንፈልገውና አቅማችንን የምንወስነውም ከልምድና ከችሎታችን አኳያ ብቻ ነው። ለእኛ ከሚስማማን ሃሳብ ጋር እናብራለን! እኛን ከሚመቸን አመለካከት ጋር እንወግናለን! የምናንፀባርቀውን ለሚያስተጋቡ ብቻ ቅድሚያውን እንሰጣለን! የእኛን እምነት ለሚያቀነቅኑ ሁሉ ሽንጣችንን ገትረን እንከራከራለን! ከዚህ ውጪ ያሉትን ሁሉንም አንቀበልም። ምንም አንጠይቃቸውም፣ ከቶም አናዳምጣቸውም፣ "ስለምን ከእኛ ለየት ያለ አቋም አራመዱ" ብለን ምክንያታቸውን ለመረዳት አንሞክርም፣ ፍሬ ሃሳባቸውን አንመረምርም። ሲጀመር ስለማይጥሙን አንሰማቸውም፣ ስለማንሰማቸው ደግሞ አናውቃቸውም፣ አንፈልጋቸውም። ውስጣችንን የሞላው የራሳችን ትርኪ ምርኪና የደጋፊዎቻችን ተመሳሳይ ድሪቶ ነው። ስለዚህ በራሳችን እውቀትና የማመዛዘን ችሎታ ልክ መጥነን ባዋቀርነው ጎጆ ውስጥ ከአጋሮቻችን ጋር ያለስጋት እየኖርን፤ ሌሎችን ግን በተለየው እሳቤያቸው ምክንያት እንጠላቸዋለን፣ እናርቃቸዋለን፣ እንሸሻቸዋለን፣ እንገዳቸዋለን፣ እናጠቃቸዋለን ወይም እንዲጠቁ ሰበብ እናመቻችባቸዋለን . . . ወዘተ የማናደርጋቸው እኩይ ነገር የለም።

ወዳጆቼ፡- ልብ በሉ! በዚህ አይነት ምስቅልቅል ውስጥ አዳዲስ አስተሳሰቦችና ለየት ያሉ ውጥኖች እንዴት ሆነው ወደ ህይወታችን ይቀርባሉ? በምን መንገድና ዘዴስ እንቀየራለን? እንዴትስ አድርገን እንማራለን? በምን ተአምርስ የእውነት እናድጋለን? ወደድንም ጠላን፤ ይህ እኛነታችንንና ውስጣዊ ገመናችንን ቁልጭ አድርጎ የሚያሳይ ፊት ለፊታችን የቆመ መስታወት ነው። ጉድፋችንን እንድናስወግድ፤ አልያም ያምርብናል ብለን ላያችን ላይ እንድንተወው እድል የሚሰጥ የመጨረሻ አማራጭ። አማራጮችን ሁሉ የማይቀበልና ግራ ቀኙን ለማዳመጥ ፍጹም ፍቃደኛ ያልሆነ ሰው፤ ራሱን በማዳመጥ ብቻ ከራሱ ጋር በፍቅር ይወድቃል፤ ከዚያ ወዲያ የሚከተለው ሁሉ የማይሆን የማይሆነው ነው አጉል ትምክህት፣ ሚዛን የማይደፋ ስብከት፣ ከእኔ ወዲያ ለአሳር እና . . . መአት መአት ስህተት ከነዝባዝንኬው . . . (ይኸኔ ነው መሸሽ አሉ!)።

እስኪ ይህንን እውነታ በጥቂት ስንኞች እንቋጥረው :-

**"ሙት ሃሳብ"**

ሃሳብ እምነትና ትልሞች
እቅድ ውጥንና ስልቶች
ፈቅደው ካልተመላለሱ
ወደው ካልተንቀሳቀሱ
ባሻቸው መንገድ ተጉዘው
ወደ ፈለጉት ተረማምደው

ከዚም ከዚያም ካልመነጩ
ወዲም ወዲያም ካልፈነጩ
በነፃነት ካልጋለቡ - ከላይ ከታች ካልፈሰሱ
ያለገደብ ካልተዘሩ - ከቅርብ እሩቅ ካልደረሱ

ሞጋች ጠያቂ ምስጢር ፈልፋይ
መካች ተጋፋጭ ተከላካይ
ለማንም የማይወግኑ
ነቅሰው የሚያሳምኑ
ተቃርነው የሚጋፈጡ
ደግፈው የማያለምጡ
ሃሳብ አፍላቂና ቀማሪ
እቅድ ነዳፊ - ተቆርቋሪ

ቅን የሚያስቡ ፍጡራን
ታጋሽ አስተዋይ ጠቢባን
በየ ማእዘኑ ተረማምደው - ከየ ሸርንቆው በርብረው
ፈቅደው አምጠው ተጨንቀው - በበጎ ምናብ አልመው
ገፍተው ካልገቡ ካልደገፉት
ፀንተው ካልቆሙ ካላገዙት

እግር ከጉልበት ተቀፍድዶ
ልሳን ከንግር ተጨምድዶ
ሃሳብ ከምናብ ተሰብስቦ
ምላስ ከከንፈር ተሸብሸቦ
በቅርብ አላሚ ተጠንስሶ
እዛው ባደረ ተድበስብሶ
ባወኩሽ ናቅሁሽ እንቶ ፈንቶ
በራስ ተቦክቶ ተፈትፍቶ

እንዴት ይሆናል በግርገር
ባልነጠረ ባዶ ግብር

አይተው ገምተው አብላልተው
ቆርጠው  ዘርዝረው መዝነው
ያልከሰቡት የጋራ እርሻ - ያልደከሙበት መዳረሻ
አያብብ ወይ አያፈራ - እንቡጥም አይሆን አይጎመራ
ዘር አይሆን ወይ አይበላ
የንክርዳድ ክምር የለው መላ

የሞተ ሃሳብ ያልዳበረ
ያበቃ ትምክት የከሰረ
ፋይዳ የለሽ የተጠላ
ያለቀ ድግስ የተበላ

ቢናገር አያምርበትም
ቢዘምር አይደምቅለትም
ቢዘራ አይፀድቅለትም
ቢፈጽም አይሰምርለትም

የራሱ ተገኘ ራእይ አልባ
ቢወቅጡት እንቦጭ የማይረባ
አያድግ አይቀይር ወይ አይተወው
እንደው ተፍጨርጨር ድከም ያለው
ክምር ገለባ አራሙቻ
የሞተ ሃሳብ መዛበቻ
ፍሬ ፈርሲኪ እንትን - ብቻ
. . .   !  . . . ጉራ ብቻ ።

ምንጭ፡ Swayamsatmeetyourself.com - All Time Short Stories
"Truth is a matter of PERCEPTION"       *
ግንቦት 2009 * አዲስ አበባ



## "ዛፍ ቆራጩ"

ከዕለታት አንድ ቀን በመንደሩ የታወቀውና እጅግ ጎበዝ የሆነው እንጨት ቆራጭ፣ ጣውላ ነጋዴዎች ዘንድ ሥራ አገኘና ዳጎስ ባለ ደምወዝ ተቀጠረ። በሥራው ሁኔታና በቀረበለት ጥቅማጥቅም ስለተማረከ በተቻለው መጠን ጠንክሮ ለመስራት አቅዶ ነበር።

በሥራው የመጀመርያ እለት አለቃው የሚሠራበትን ቦታ አዟዙሮ ካሳየው በኋላ አንድ እንጨት መቁረጫ ፋስ ሰጠው። የዚያን ቀን አስራ ስምንት ዛፎችን ቆርጦ አስገባ። አለቃው በጣም ደስ አለው። "በርታ በዚህ ቀጥል" በማለት አበረታታው። በአለቃው ሙገሳ የተበረታታው እንጨት ቆራጭ፣ በሚቀጥለው ቀን በጣም ጠንክሮ መስራቱን ቀጠለ፡፡ ይሁን እንጂ ማምጣት የቻለው አስራ አምስት ዛፎች ብቻ ነበር። በሦስተኛው ቀን የበለጠ ለመቁረጥ ቢጥርም ከአሥር ዛፎች በላይ ማስገባት አልቻለም። በዚህ አይነት በየቀኑ ቆርጦ የሚያስገባቸው ዛፎች ቁጥር እያነሰ እያነሰ መጣ።

እንጨት ቆራጩ በሁኔታው ግራ ተጋባ። በዚህ ከቀጠለ ሥራውን እንደሚያጣ በማሰብ ተጨነቀና ወደ አለቃው ቀርቦ እንዲህ አለው "ይቅርታ አድርግልኝ፣ ከምንጊዜውም በላይ ከልቤ በመነጨ ስሜትና ፍላጎት የማገልገል ተነሳሽነት ነበረኝ። ነገር ግን ምን እንደነካኝ አላውቅም፣ ከጊዜ ወደ ጊዜ አቅሜን እያጣሁ መጥቻለሁ" በማለት ነገረው።

አለቃውም፤ "ለመሆኑ ፋስህን ለመጨረሻ ጊዜ የሞረድከው መቼ ነው?" በማለት ጠየቀው።

"የሞረድከው? ምን ጊዜ አግኝቼ! ትኩረቴ በሙሉ ዛፎቹን በመቁረጥ ላይ ስለነበር . . . " አንገቱን አቀርቅሮ ዝም አለ። ይባላል።

ክንዶቹን ሽቅብ እያነሳ በመላ ኃይልና ጉልበቱ ፋሱን ግንዱ ላይ ያሳርፋል፤ ግን አይቆርጥም። ልፋትና ድካሙን የደነዘው ፋስ ያመክነዋል። ፋሱን ለመሞረድ የሚያጠፋው ጥቂት ጊዜ እያሳሳው ባለማወቅ ሙሉ ቀኑን ያባክናል።

የእያንዳንዳችን ህይወት ከዚህ ጋር ይመሳሰላል። አንዳንዴ እጅግ በጣም በሥራ እንጠመድና "ፋሱን እንደ መሞረድ" ለራሳችን የሚሆን ምንም ጊዜ እናጣለን። ውጣ ውረድ በበዛባት በዚህ ባለንበት ዘመን፣ ሁላችንም ከምንጊዜውም በላይ ብንታትርና ብንለፋም የምናገኘው ደስታ እያደር የሚቀንሰው ለዚህ ይመስለኛል።

ይህ ለምን ሆነ? ወቅቱን ጠብቀን መሞረድ በመርሳታችን ስለቱ እንዲደንዝ አድርገን ይሆን? . . .

በሥራና እለት ተእለት በምናደርገው የኑሮ ጥድፊያ ውስጥ ምንም ስህተት የለም። ነገር ግን በምናደርገው የበዛ ወከባና ሩጫ የዘነጋናቸውና በእውነት ልንከታተላቸው ሲገባ ትኩረት የነፈግናቸው ወሳኝ ኹነቶች አሉ። ለምሳሌ ለፈጣሪያችን፣ ለግል ህይወታችን፣ ለቤተሰቦቻችን የምንሰጠው ቦታ እንዲሁም ለማመስገን፣ ለማንበብ፣ ለማረፍና ለመዘጋጀት የምንመድበው ጊዜ በሥራ በዛብኝ ሰበብ እየሚሸሸ መሄዱ አብይ ሳንካ ሊሆን ይችላል።

ሁላችንም ከሠራን ለማረፍና ለመዝናናት በቂ ጊዜ መመደብ ይጠበቅብናል፣ ለራሳችን የተሟላ የጥሞና ጊዜ በመስጠት ጎሊናችንን ማዳመጥ ይገባናል፣ ለመማርና ግንዛቤአችንን ለማስፋት ተገቢውን ትኩረት መለገስ ያስፈልገናል። በጊዜ ያልተሞረደው "ፋስ" ስለቱን አጥቶ - ደንዟል። እኛም ይህንን ካላደረግን ብቃትና ውጤታማነታችን ጥሎን ሄዶ፣ ውጤት የለሽና እርባና ቢስ ሆነን እንቀራለን።

የኛ ሞረድ በተገቢው ሰዓት ለራሳችንና ተያያዥ ሁኔታዎች የምንሰጠው የእረፍት፣ የዝግጅት፣ የውይይት፣ የምስጋና፣ የማጠናከርያ፣ የመማርያና የማሰብያ . . . ወዘተ ጊዜ ነው። ስለዚህ እላችኋለሁ፤ "ሞረዱን ካጠገባችን ሳናርቅ፣ ዘውትር ሳንዘናጋ እየሞረድን - ስለታችን እንደሰላ ጥንካሬአችን፣ ብቃታችን፣ ብርታታችንና ጽናታችን እንደተጠበቀ በውጤታማነት እንኑር !።

ደራሲ ፡ ስቴፈን ኮቪይ (Stephen Covey)
ምንጭ ፡ "7 Habits of Highly Effective People" መጽሃፍ

የካቲት 2007 *** አዲስአበባ





## ገፀ በረከት!

ልጁ የዩኒቨርሲቲ ትምህርቱን ለማጠናቀቅ የቀረው ከሁለት ወራት ያነሰ ጊዜ ነው። ዘንድሮ በከፍተኛ ትምህርት ተቋሙ ውስጥ ለተከታታይ አምስት ዓመታት የደከመበትን የልፋት አዝመራ የሚያጭድበት እንደመሆኑ ዘመኑ ለሱ ልዩ ነበር። በተለይ ለምረቃው አባቴ ይሰጠኛል ብሎ የሚጠብቀው ማራኪ ስጦታ እንቅልፍ ነስቶታል። ባለፈ ባገደመ ቁጥር የሚቃኛትና በኩባንያው የሽያጭ ማሳያ ክፍል ውስጥ ፊት ለፊት የምትታየው ቀይ የስፖርት መኪና በየንግግሩ ጣልቃ የማትጠፋ ሆናለች፤ ከአባቱ የመግዛት አቅም ጋር እየመዘነ በምረቃው ዕለት ትበረከትልኛለች በሚል ተስፋ ተሞልቷል።

የምረቃው ቀን ጠዋት ወደ አባቱ የግል ንባብ ክፍል እንዲመጣ መልክት ደረሰው፤ እየተቻኮለ ወደ ውስጥ ገባ። አባቱ በጥልቅ የደስታና እርካታ መንፈስ ተሞልቶ ተቀበለው፤ "ውድ ልጄ አኮራኸኝ - ኮራሁብህ! እንዳንተ አይነት የተባረከ ትጉህ ልጅ የሰጠኝን አላህ ደጋግሜ አመሠግነዋለሁ። ልጄ እወድሃለሁ - ምንጊዜም እወድሃለሁ!!" የእንባ ሣግ እየተናነቀው እቅፍ አድርጎ ሳመውና በብልጭልጭ የስጦታ ወረቀት የተሸፈነ ትንሽ አራት ማእዘን ሳጥን እጁ ላይ አስቀመጠለት።

በጉጉት እየተጣደፈ ስጦታውን ከፈተው፤ ባማረ የቆዳ ሽፋን የተጠረዘ <u>ቅዱስ ቁርአን</u> ነበር። የወጣቱ ዓይኖች በንዴት ተንቀለቀሉ፤ አፉ ደርቆ ስጦታውን የያዙት እጆቹ ይንቀጠቀጡ ጀመር። ድምጹን ከፍ አድርጎ መናገር የቻለው "ከዚህ ሁሉ ገንዘብህ ልትሰጠኝ የቻልከው አንድ ቁርአን ብቻ ነው?" የሚል ነበር። ወዲያው ቅዱስ ቁርአኑን ጠረጴዛው ላይ አስቀምጦ እንደ ነፋስ ተሽቀንጥሮ ቤቱን ለቆ ወጣ።

ከዚያን ጊዜ ወዲህ ወደ ቤቱ አልተመለሰም። አባቱንም አይቶት አያውቅም። ብዙ ዓመታት አለፉ። ወጣቱ ልጅ ባለበት ቦታ ነገሮች የተሳኩለት ሆነ፡፡ የተዋጣለት የንግድ መሪ፣ ባለብዙ ሃብትና ንብረት ባለቤት፣ አስደሳች ቤተሰብ የመሰረተ ውጤታማ ሙሉ ሰው ወጣው። እየዋለ ሲያድር ልጅ አባቱን ማየት ፈለገ፣ ከዚያች የምረቃ እለቱ ወዲህ አይቶት የማያውቀው አባቱ፤ ምን ያህል ሊያረጅና ሊደክም እንደሚችል በዓይነ ኅሊናው እየሳለ፣ አባቱን የመጠየቅ ጉጉቱን ስላናረበት ለጉዞው መዘጋጀት ጀመረ።

ይህ በእንዲህ እንዳለ አንድ ጠዋት አባቱ ከዚህ ዓለም በሞት መለየቱን የሚያረዳና የጠቅላላ ሃብቱ ወራሽ ሆኖ በቅርበት ይመራ ዘንድ በአስቸኳይ እንዲመጣ የሚገልጽ የቴሌግራም መልዕክት ደረሰው። ወዲያው ተነስቶ ጉዞውን በመጀመር ረጅሙን መንገድ በግማሽ ቀን አገባዶ በከፍተኛ ፀፀት፣ ሃዘንና ሠቀቀን እንደተዋጠ ለዘመናት ከተለየው የአባቱ ቅጥር ግቢ ደረሰ። ጊዜ አላባከነም፡፡ የአባቱን ዋና ዋና ሠነዶች ለመመልከት ወደ አባቱ የግል ንባብ ክፍል ገባ። የጥፋተኝነት መንፈስ ወረረው . . . ቀስ ብሎ ወደ ጠረጴዛው ተራመደ፣ ዓይኑን ማመን አልቻለም፤ ከዓመታት በፊት ጠረጴዛው ላይ አስቀምጦት የሄደው ቅዱስ ቁርአን በነበረበት ተቀምጧል። እንባው - ግድቡን እንደጣሰ ጅረት ፊቱን እያራሰው፣ በብዥታ ውስጥ በሚንቀጠቀጡት እጆቹ ቅዱስ ቁርአኑን አነሳና ወደ ደረቱ አስጠግቶ ያዘው . . . ። ቀና ሲል ግድግዳው ላይ የተሰቀለው የአባቱ ፎቶግራፍ ፈገግ ያለ መሰለውና ደንግጦ አንገቱን ደፋ፣ በዚህ መሃል ከቅዱስ ቁራኑ ውስጥ የመኪና ቁልፍ ዱብ ብሎ ወደቀ። ጎንበስ ብሎ አነሳው፣ ካርድ ተንጠልጥሎበታል . . . በላዩ ላይ "ልጄ እንኳን ደስ አለህ!" የሚል የእጅ ጽሁፍ በጉልህ የሚታይ ሲሆን፣ የመኪና ሽያጭ ደረሰኝና ዝርዝር መግለጫ ሆኖ ከግርጌው "ሙሉ ለሙሉ የተከፈለ" የሚል ማህተም ተደርጎበታል። (ቀኑ የምረቃው እለት ነበር) መኪናዋም ያችው ሲያልማትና ሲመኛት የነበረችው፣ ያችው ከአባቱ ጋር ለመለያየቱ ሰበብ የሆነችው የስፖርት መኪና ነበረች።

አቤት! የመከራ ቀን መርዘሙ። እቶን የቁጭት ወላፈን፣ ሸክሙ የከበደ የፀፀት መርግ፣ የማያከሙት የህሊና ቁስል፣ እንባ ማይሽረው የሕይወት ጠባሳ . . . ። ምን ይበል? ይኼ ነው ችኮላ። ይኼ ነው ሳያረጋግጡ የመወሰን የሁላችንም በሽታ። ይኼ ነው በጭራሽ ልንመልሰ ወደማንችላቸው የስህተት ድምዳሜዎች እያጣደፈ የሚያደርሰንና ለፀፀት የሚዳርገን አጉል ባህሪይ።

እኛስ . . . በምንጠብቀው አይነት ስላልተጠቀለለ ብቻ፣ የምንፈልገው አይደለም ብለን ስንት ጊዜ ስጦታችንን ወርውረናል? ስንት ጊዜ መከሊታችንን ገፍተናል? ስንት ጊዜ በረከታችንን ንቀናል? ስንት ጊዜ፣ . . . ስንት ጊዜ?

**<u>"እኛ እንግዲህ - እንደዚህ ነን"</u>**

እኛ እንግዲህ - እንደዚህ ነን - ሠዎች ስንባል ፍጡራን
ያላዋቂ - ጥበበኞች - የአለም ዘዋሪ ድኩማን።

ሳንረዳ እያወቅን - ሳንመረቅ የመጠቅን
ሳንተኛ እያለምን - ሳንሯሯጥ የቀደምን
ሳንቆጥር የደመርን - ሳንደቁን የቀሰስን
ሳንወለድ እያደግን - ሳንታገል የወደቅን
በወለፈንድ የምንኳትን - ትግስት አተን - የምንባዝን።

እኛ እንግዲህ - እንደዚህ ነን - ሠዎች ስንባል ፍጡራን
ያላዋቂ - ጥበበኞች - ያለም ዘዋሪ ድኩማን።

ሳንመዝን ሳናጣራ - ጠልቀን ሳናይ - ሳንመረምር
ሳናስተውል ሳንፈትሽ - አደብ ገዝተን - ሳንመክር
በራስ ግብር - ከመጨነቅ - መሸ ነጋ ከመፀፀት
ባለፈ ውል - ከማማረር - ላይመለስ ከመቆጨት
እርምጃችን - የተጠና - ውሳኔአችን የረቀቀ
ለህሊና - የተገዛ - ከ ሃቅ ደጅ የፈለቀ



ይሆን ዘንዳ - እንረዳ - ባምላክ ፀጋ የደመቀ ፡፡
ይሆን ዘንዳ - እንረዳ - ባምላክ ፀጋ የደመቀ ፡፡

ምንጭ ፡- 100 Moral Stories Collection by Akramulla Syed
ታህሳስ - 2007 * አዲስ አበባ

## **<u>አርበኛው - (አጣ ፈንታ)</u>**





ጃፓናዊው አርበኛ እጅግ ከባድ ፍልሚያ ከፊቱ ተደቅኗል። በውግያ ጥበቡ ወደር የለሽ የተባለው ሥመ ጥር ጀግና ኦዳ ኖቡናጋ ወደ ጦር ግንባር ሲጓዝ የሚታይበት ፍጹም እርጋታና የቆራጥነት መንፈስ በዘጠኝ እጥፍ ከሚበልጡት የጠላት ወታደሮች ጋር የሚጋፈጥ አይመስልም ነበር። እጅግ በሰላና ውስብስብ በሆነው የውግያ እቅዱ ይተማመናል፣ ጦርነቱን በድል እንደሚያጠናቅቅም እርግጠኛ ነው። ወታደሮቹ ግን አይደሉም፣ ጥርጣሬ ገብቷቸዋል።

ይህንን የተረዳው የጦር መሪ ወታደሮቹን አሰልፎ በሽንቶ ቅዱስ ሥፍራ አጠገብ በማለፍ ላይ ሳለ፤ ወታደሮቹ እንዲቆሙ ትእዛዝ አስተላለፈ። ሁሉም በተጠንቀቅ መቆማቸውን ካረጋገጠ በኋላ እንዲህ አላቸው . . . "ውድ አርበኛ ጓዶቼ! አሁን ወደ ቤተ መቅደሱ ገብቼ እፀልያለሁ፣ ከዚያም አንድ ሳንቲም አውጥቼ ወደ ላይ እወረውራለሁ፣ ንጉስ ከወጣ ጦርነቱን እኛ እናሸንፋለን ካልሆነ ግን በተቃራኒው ተሸናፊ ነን። ወንድሞቼ እንግዲህ ድሉን እድል ይወስነዋል። ሁሉም ነገር በእጣ ፈንታ መዳፍ ላይ ወድቋል" አላቸውና ወደ ቤተ መቅደሱ ገባ።

ፀሎቱን አጠናቆ ከፊት ለፊታቸው ቆመና ሳንቲሟን ወደ ላይ ወረወራት። እየተሽከረከረች ሽቅብ ሄደችና ቁልቁል ተመልሳ መሬቱ ላይ ተንከባላ . . . ተንከባላ በመጨረሻ አረፈች። ግሩም ውጤት! ንጉስ ከላይ ታየ። የወታደሮቹ ጩኸት አስተጋባ፣ እርስ በእርስ መተቃቀፉ፣ በደስታ መዝለሉ፣ በወኔ መፎከሩና መሸለሉ፤ አካባቢውን አደመቀው። ከዚያ ወዲያማ በብሩህ የድል ተስፋ የተሞሉት ወታደሮች ጠላትን ድባቅ ለመምታት ባደረባቸው ጥልቅ የራስ መተማመን ስሜት የጦርነቱን ጅማሮ በጉጉት ይጠባበቁ ጀመር።

ቀናት አልፈው፣ ጦርነቱ በድል ተጠናቆ፣ ሁሉም ነገር ከሰከነ በኋላ ከእለታት በአንዱ የእረፍት ቀን የጦሩ ዋና መሪ ኖቡናጋ ሳን እና ምክትል አዛዡ ጎን ለጎን ተቀምጠው ሳኪ እየተጎነጩ ያወጋሉ። በመጨረሻ ስላደረጉት የጦርነት ውሎ አስታወሱና ምክትል አዛዡ እንዲህ አሉ . . . "ጌታዬ - እኔ የእድል ነገር በጣም እንዳስገረመኝ ነው፤ ማንም ቢሆን - በምንም አይነት እጣ ፈንታን መቀየር እንደማይችል ተገንዝቤአለሁ" በማለት ግርምታቸውን አነሱ።

አርበኛው ኖቡናጋ ሳን የምክትል አዛዡን ንግግር ከሰማ በኋላ "በፍጹም አይደለም!" በማለት ጮክ ብሎ መለሰላቸው። ከዚያም ፈገግ ብሎ ወደ ረዳቱ እየተመለከተ ያኔ ከጦርነቱ በፊት ወደ ላይ የተወረወረችውን ሳንቲም ከኪሱ አወጣትና አሳያቸው። . . . ልዩ ነች። በሁለቱም በኩል ንጉስ። አይይ እጣ ፈንታ።

ውስጣዊ እምነት እርግጠኝነትን አጠናክሮ፤ ለድል እንዴት እንደሚያበቃ አያችሁልኝ።

(የሽንቶ ቅዱስ ስፍራ፡- የጃፓናውያን የእምነት ቦታ))
(ሳን፡- የሚለው ቃል ከሥም ለጥቆ የሚገባ የአክብሮት መጠርያ ነው)
(ሳኪ፡- የጃፓኖች ባህላዊ የአልኮል መጠጥ ነው)

ምንጭ: m www.moralstories.org
ሚያዝያ - 2008 ዓ.ም.



## "ይደር - ይቀመጥ"

መምህሩ በእጁ አንድ ብርጭቆ ውሃ ይዞ ከተማሪዎቹ ፊት ለፊት ቆሟል። እጁን ከፍ አድርጎ ለተማሪዎቹ በማሳየት "የዚህ ብርጭቆ ክብደት ምን ያህል ይመስላችኋል?" በማለት ጠየቃቸው።

"50 ግራም . . . 100 ግራም . . . 250 ግራም . . ." በማለት የተለያየ ግምታቸውን ሰጡ።

መምህሩም "ካልተመዘነ ትክክለኛ ክብደቱ አይታወቅም በዋናነት እኔ ልጠይቃችሁ የፈለግሁት "የቀኝ እጄን ወደ ላይ ከፍ አድርጎ "በዚህ አይነት ለጥቂት ደቂቃ ብቆይ ምን የሚሆን ይመስላችኋል?" ሲል ጠየቃቸው።

"ምንም አይሆንም" በማለት መለሱለት።

"ለአንድ ሰዓት ብቆይስ?"።

"የቀኝ ክንድህ ላይ ህመም ይሰማሃል" ሲል ከተማሪዎቹ አንዱ መለሰለት።

"ትክክል ነው፣ ለአንድ ቀን ያህል ብቆይስ?" በማለት ጠየቃቸው።

አንድ ተማሪ ተነሳና "መምህር ለአንድ ቀን ቢቆዩ በመጀመሪያ እጅዎ ይደነዝዛል፣ በመቀጠል ከፍተኛ ህመምና የጡንቻ መወጠር ይከተላል፣ ከዚያም የማይቋቋሙት የአካል ዝለት ይፈጠርና በእርግጠኛነት! እርስዎን ወደ ሆስፒታል መውሰድ ይጠበቅብናል" ሲል መላው ተማሪ በሳቅ አውካካ።

መምህሩም - "በጣም ጥሩ፤ በዚህ ሁሉ ጊዜ ውስጥ የብርጭቆው ክብደት ተቀይሯል?" ሲል ጠየቃቸው።

"አልተቀየረም" በማለት መለሱለት።

መምህሩም - "ታድያ የክንድ ህመም፣ የጡንቻ መደንዘዝና መዛል ችግር ከየት መጣ ?"

ተማሪዎቹ በዝምታ ተዋጡ።

"መፍትሄውስ ምንድን ነው ?"

አንድ ተማሪ ተነሳና "ብርጭቆውን አውርዶ ማስቀመጥ" አለ።

መምህሩም - "ትክክለኛው ድርጊት ይህ ነው። ብርጭቆውን መልሶ ማስቀመጥ፤ ተሸክመነው በቆየን ቁጥር የመሸከም አቅማችን ሲቀንስ፣ ክብደቱ እየጨመረ ይመጣልና ለተወሰነ ጊዜ በማረፍ እንደገና ለማንሳት በቂ ሃይል ማጠራቀም ያስፈልጋል።

ልብ በሉ! የህይወት ችግሮችም ከዚህ ጋር ተመሳሳይ ናቸው። ለተወሰነ ጊዜ በአእምሯችን ልንይዛቸው እንችላለን በውስጣችን እያብላላን ባቆየናቸው ቁጥር ግን ችግሮቻችን እየተወሳሰቡ፣ በጭንቀት እየተዋጥን፣ አቅማችን እየዛለ፣ ውጥረቱ እየሰፋ፣ ሚዛናዊ አስተሳሰባችን እየደነዘዘ፣ ህመሙም እየጨመረ ይሄድና ለከፋ የአእምሮ ውጥረትና ጭንቀት ከመዳረግ አልፎ ወደማያገግም የጤና እክል ሊያመራ ይችላል ።

በኑሯችን ውስጥ የሚገጥሙን ችግሮችና መሰናክሎች ሁሉ እያንዳንዳቸው የራሳቸው የሆነ የቦታና የጊዜ መርሃ እሳቤ ሊኖራቸው ይገባል። ቀን በስራ ገበታችን ላይ የገጠሙንን ችግሮች እንደተሸከምን ወደ ቤት ከገባንና ሳናራግፋቸው ወደ መኝታችን ከሄድን፤ ሌቱን እንቅልፍ አጥተን ስናብላላቸው ይበልጥ ተወሳስበውና ከብደው ከቤትና ከአዳራችን ጨምረው በነጋታው ምን ያህል በእረፍት እጦት የደከመና የተንሳቀለ አእምሮ ይዘን እንደምንወጣ መገመት አያዳግትም።

የችግሮቻችን አይነቶች እንደ መልካችን የመለያየታቸውንና የመብዛታቸውን ያህል መንስኤዎቻቸውና መፍትሄዎቻቸውም የዛኑ ያህል በርካታና እንደ እያንዳንዳችን ጥንካሬና የአያያዝ ብቃት የሚመዘኑ ናቸው። እዚህ ላይ ብቃታችን የሚለካው ችግሩን ተሸክመን በምንቆይበት ጊዜ ነው። እንደሁኔታው አውርደን በማስቀመጥ በቂ እረፍት የምንወስድ ከሆነ ብቁና ጠንካራ ስንሆን ይዘነው የምንቆይና ስናብሰለስለው የምናድር ከሆንን ግን መጪውን ለመቀበል የማንችል ደካማና ተሸናፊዎች እንሆናለን። ስለሚገጥሙን መሰናክሎችና ችግሮች ማሰባችን ተገቢ ነው። እጅግ አስፈላጊውና ዋናው ነገር ግን ከመተኛታችን በፊት አውርደን ማስቀመጥ ነው፤

በዚህ አይነት መንገድ ኑሯችንን ከመራን በየእለቱ  ከጭንቀትና ከሃሳብ ነፃ ሆነን የማለዳዋን ፀሃይ ዘና ባለ ጠንካራ መንፈስ በመቀበል የትኛውንም አይነት ችግር ለመቋቋም ማናቸውንም አይነት ፈተናዎች ለማለፍ ብቁና ዝግጁ እንሆናለን።

ምንም ይሁን ምን - የታሪኩ አስኳል ቁም ነገር በየእለቱ በሥራ ቦታችንና ውሏችን የሚገጥሙንና መፍትሄ ያላገኘንላቸውን ችግሮች፤ በአእምሯችን እንደያዝን ወደ ቤታችን ከተመለስን ይብስ ደግሞ ወደ መኝታችን ከሄድን ብርጭቆውን ተሸክሞ እንደዛለው ክንዳችን - አእምሯችንም ከፉኛ የዛለና የደከመ ይሆናል። ነገር ግን በሥራ ቦታችን መፍትሄ ያላገኘንላቸውን ችግሮች እዚያው አውርደን በማስቀመጥ አእምሯችንን አሳርፈን በነጋታው በብቃት ካስቀመጥንበት ልናነሳቸው እንችላለን። በቀሪው ውሏችንና ምሽታችን ያጋጠሙንን ደግሞ ወደ መኝታችን ከመሄዳችን በፊት አውርደን በማስቀመጥ፤ ቀጣዩን ቀን በቂ እረፍት ባገኘ ብሩህ አእምሮ በመጀመር ውሏችን ስኬታማ ይሆናል የሚለው ነው።

ምንጭ፡   - ከማኅበራዊ ድረ ገጽ - ቆየት ያለ ምሳሌያዊ ወግ - (የሕዝብ)
ግንቦት - 2006 - አዋሳ

**ምርመራ**



እድሜው ከ አስራ ስምንት የማይዘል ለግላጋ ወጣት ነው። ራመድ ራመድ እያለ ከመንገዱ በስተግራ በሯ ወለል ብሎ ወደተከፈረው ሱቅ ገባና ከባንኮኒው በስተጀርባ ወደተቀመጡት ሰው እየተመለከተ "ስልክ መደወል ፈልጌ ነበር" አላቸው። ነጭ ዳንቴል ለብሶ መደርደርያው ላይ የተቀመጠውን ጥቁር ስልክ አንስተው ጭናቸው ላይ አስቀመጡና ቀና ብለው አዩት። (ጊዜውን አረፍተ ነገሩ ስለገለፀው መጥቀስ አያስፈልግም)። ሰባት ቁጥሮችን በዝግታ ነገራቸው . . . አዙረው አዙረው ሲያበቁ መነጋገሪያ እጀታውን ተንጠራርተው አቀበሉት። የተቀባዩ ድምጽ ለባለሱቁ አዛውንት በደንብ ይሰማ ነበር።

ልጁ - "የኔ እመቤት የግቢዎን ሳር የማጨዱን ሥራ ለኔ ሊሰጡኝ ይችላሉ?" ጠየቀ።

ሴትየዋም - "አዝናለሁ! አጨዳውን ሌላ ሰው ወስዶት እየሰራው ነው" መለሱለት።

ልጁ - "እባክዎን እኔ የማጨዱን ሥራ አሁን ከሚያሰሩበት ዋጋ በግማሽ ቀንሼ እሰራሎታለሁ" አላቸው።

ሴትየዋም - "አሁን እያጨደልኝ ባለው ሰው ሥራ እጅጉን ረክቻለሁ፣ እናም ሌላ ሰው አልፈልግም" መለሱለት።

ልጁ - በጉጉት ስሜት "የእኔ እመቤት ከአጨዳው ሌላ ጽዶቹንና የጠርዝ ላይ አትክልቶቹን ሁሉ እከረክማለሁ፣ በተጨማሪ የውስጥ ለውስጥ መንገዶቹን በማጽዳትና መላ ቦታውን በመንከባከብ ፍሎሪዳ ውስጥ ማንም የማይስተካከለው እጹብ ድንቅ መስክ አደርገዋለሁ" አላቸው።

ሴትየዋ - ረገጥ አድርገው "በምንም አይነት አይሆንም! ስለጥረትህ አመሰግናለሁ!" አሉት።

ልጁም - በትህትና "እኔም አመሰግናለሁ" አለና ፈገግታው ከፊቱ ላይ ሳይጠፋ እጀታውን ለባለ ሱቁ መለሰላቸው።

ሰውየው በአድናቆት እየተመለከቱት ከባንኮኒው ወጡና ያነጋግሩት ጀመር። "ልጄ ትህትናህ፣ ለሥራ ያለህ ፍቅርና ቀና አመለካከትህ ልቤን ነክቶታል። እንደ አንተ አይነት ሰዎች እጅግ ጥቂት ናችሁ። እባክህ እኔ ሥራ ልሰጥህ እፈልጋለሁ?" አሉት።

ልጁ - "አባቴ - እኔ ሥራ አልፈልግም፤ አመሰግናለሁ" በማለት መለሰላቸው።

ባለ ሱቁ - "አሁን አንዲት ሥራ ለማግኘት ስትጠይቅና እንደውም በግማሽ ለመሥራት ስትደራደር መስማቴን እርግጠኛ ነኝ! ታድያ ምንድነው እምቢታህ?" በማለት ጠየቁት ።

ልጁም - "አይደለም አባቴ! እኔ ብቃቴን እየመረመርኩ ነበር፣ በተሰማራሁበት ሥራ ላይ ያለኝን ጥንካሬና ተፈላጊነት ለመመዘን እንጂ የአጨዳውን ሥራኮ በመስራት ላይ ያለሁት ሰው እኔው ነኝ" አላቸው። ይባላል።

ወዳጆቼ! እራስን መፈተሽ ማለት እንደዚህ ነው። ሁሌም ሌሎችን እንኮንናለን፣ የምናማርረውና ሰበብ የምናደርገውም ሌላ ሌላውን ነው። ይህ ወደ ራሳችን ማየትና ማወዳደር፣ ስህተትና ደካማ ጎኖችን ነቅሶ ማረም እንዲሁም አዩኝ አላዩኝን ትቶ በቅን ልቦና ጠንክሮ መሥራት . . . ለዘወትር የሚተርፈን ብቸኛ መርህ ነው - እንያዘው።

 Moral Stories.com (Motivation page) - “Boy’s Job Appraisal”
ሃምሌ 3 2009 ዓ.ም. - አዳማ



## በጎነት

አቶ ደቻሳ ዘወትር እንደሚያደርገው ሁሉ በጠዋት ተነስቶ ወደ ሥራ ለመሄድ ዝግጅቱን አጠናቋል። ባለቤቱ ጥቂት እንዲጠብቃት ነገረችውና ጓዳ ገብታ አንድ የተጣጠፈች ቢጫ ወረቀት ይዛ ተመለሰች። ወዲያው እየሰጠችው "እባክህ ዛሬ ማታ ከሥራ ስትመለስ የምታወጣው ነው" አለችው። እጥፋቷን ፈታና ጎንበስ ብሎ አነበባት "ሽሪፍ የልብስ ንጽህና መስጫ ደረሰኝ" ይላል። "የማን ነው? ይህን ያህል አስቸኳይ ነው እንዴ?" አላት። ባለቤቱም "ሠራተኞችን አረጋሽ ቤተሰቦቿን ለመጠየቅ ነገ ወደ ገጠር ትሄዳለች፣ የመጀመሪያውን አውቶብስ ለመያዝ የምትወጣው ማለዳ ሲሆን እዚያ ለሁለት ቀን ያህል ትቆያለች" በማለት ስትመልስለት "ምነው? ምን ገጠማትና ነው የምትሄደው? በማለት ጠየቃት። "አሁን የምትሄደው የመጀመርያ ልጇን የበኩር ልጅ አንደኛ ዓመት የልደት በአል ተሰባስበው ለማክበር ሲሆን አደራህን ልብሱን እንዳትረሳ በጣም አስፈላጊ ነው" አለችው። እርሱም "ችግር የለም አታስቢ" አላትና እቅፉ ውስጥ እንዳለች ግንባሯን ስሞ ደረጃውን ወረደ።

ከኋላው "ደቺዬ. . . ደቺዬ" ብላ ስትጠራው ሰማና መለስ ብሎ ጠበቃት። "አንድ የረሳሁት ነገር አለ፤ እባክህ? ለአረጋሽ የ300 ብር ጉርሻ ልሰጣት ፈልጌ ነበር፤ እንደው ለአንዳንድ ነገሮች ይሆናታል ብየ ነው?" አለችው አቀርቅራ መሬት መሬት እያየች። "የኔ ውድ እጅግ ሩህ ሩህ መሆንሽን ባውቅም ትንሽ አይበዛም ለአዲስ ዓመት ሰጥተናታልኮ?" አላት።

እሷም "አየህ ይሄኛው ከበፊቱ ይለያል ልደቱን ለማክበር የምታወጣው ወጪ ብዙ ነው። በዚያ ላይ ከልቧ የምትሠራ ታታሪ ሴት ናት" አለችውና አያይዛ "ለተጨማሪ ወጪው አታስብ ቃል የገባህልኝን የፒዛ ግብዣ በመሰረዝ ሁለት መቶ ሰማንያ ብሩን ማትረፍ እንችላለን" አለችው። ደቻሳ ትኩር ብሎ አያት፣ በሚስቱ ሰብአዊነት ሁሌ እንደኮራ ቢኖርም የኳኋለትን ፒዛ ከአፉ ውስጥ ያወጣችበት መሰለውና ተከዘ። ወዲያው ቦሌ መንገድ ታዋቂ በሆነው ምግብ ቤት ውስጥ በሚወደው ስፐራይት የሚያወራርደውን ስፔሻል ፒዛ ከሚስቱ ደግነት ጋር በማወዳድር፤ ፈገግ ብሎ ወደ ሚስቱ ዞረና . . . "አይዞሽ ሁሌም በጥሩነትሽ ቀጥይ፣ ያሰብሽው ገንዘብም ይኸውልሽ" በማለት ከቦርሳው አውጥቶ ሰጣት።

ከሁለት ቀናት በኋላ አረጋሽ ከሄደችበት ተመልሳ ወለሉን በማጽዳት ላይ ነበረች፣ አቶ ደቻሳ ወደ ቤት እየገባ አያትና . . . "እንኳን ደህና መጣሽ! እንዴት ነበር ልደቱ? ከልጆችሽ ጋር ጥሩ ጊዜ አሳለፋችሁ?" በማለት ጠየቃት። እሷም "ሁሉም ነገር በጣም ጥሩ ሆኖ አለፈ፣ እድሜ ለእናንተ እጄ ሙሉ ነበር፣ የሰጣችሁኝን 300 ብር በሚገባ ተጠቀምኩበት" ስትለው ዝርዝሩን ለማወቅ ጓጉቶ "እንደው እንዴት እንዴት አብቃቃሽው" አላትና እንደሚከተለው መለሰችለት . . .

1ኛ. 70 ብር ቀሚስ ለባለ ልደቷ የልጅ ልጄ
2ኛ. 20 ብር ለጣፋጭ ከረሜላ
3ኛ. 50 ብር ለደርሶ መልስ ትራንስፖርት
4ኛ. 40 ብር ለትልቋ ልጄ ነጠላ ጫማ
5ኛ. 25 ብር ካልሲ ለወንዱ የልጅ ልጄ
6ኛ. 35 ብር ቀበቶ ለእንጀራ ልጄ ልጅ
7ኛ. 25 ብር ለልጄ ጓደኛ የታክሲ
8ኛ. 35 ብር ሁለት ደብተር፣ ሁለት እርሳስና አንድ እስኪሪብቶ ገዝቼላቸው ስገባ አቤት የተሰማኝ እርካታ፣ የእነርሱ ደስታ ደግሞ ለመግለጽ የሚከብድ ነበር"። አለችው።

አቶ ደቻሳ በግርምት እንዳፈጠጠ በሃሳብ ጭልጥ ብሎ ሄደ . . . ሄደ . . . ሄደና በምናቡ አንዱን ፒዛ በማንሳት ስምንትት ባለ ሶስት ማእዘን ቁርጥራጮች አወጣለት፣ ከዚያም የአረጋሽን ስምንት የተለያዩ ጉዳዮች በእያንዳንዱ ቁራጭ ላይ አስቀመጦ ሲያበቃ በኅሊናው መዘናቸው። ልክ በዚያች ቅጽበት ለኛ ቀላልና ምንም የማይመስሉን ልግስናዎች ሌሎችን ምን ያህል ሊጠቅሙ እንደሚችሉ ፍንትው ብሎ ታየው። አረጋሽ በፍጹም ደስታ ያሳለፈቻቸው ሁለት ቀናት፣ በስጦታ የተንበሸበሹት ልጇ፣ የልጅ ልጆቿና የመላ ቤተሰቡ እርካታ ሁሉም . . . ሁሉም በቃ በሁለት ፒዛዎች ዋጋ ነበር። የዚያን እለት አንድ ትልቅ ነገር ተገነዘበ።

ወዳጆቼ ! - ሁላችንም ይብዛም ይነስ የሻትነውን ደስታ እናገኝበታለን ብለን ለፈቀድነውና ለመሰለን ጉዳይ ደክመን ያመጣነውን ገንዘብ ማውጣታችን ያለና የእያንዳንዳችን መብት መሆኑ የሚያጠያይቅ አይደለም። ይሁን እንጂ አልፎ አልፎም ቢሆን ያገኘነው ደስታ፣ እርካታ፣ መዝናናትም በሉት ፈንጠዝያ ካስመነዘረን የገንዘብ መጠን ጋር ብቻ ሳይሆን ከውጤቱም ጭምር እንመዝን ዘንድ፤ እንደ አቶ ደቻሳ የሚያዳምጥና እንደባለቤቱ የሚያገናዝብ ቀና ልቦና ግድ ይላል። እስቲ ዘወትር በቋሚነት የምናባክነው ገንዘብ እንዳለ ሆኖ፤ በአለፍ ተገደም ከኪስ ቦርሳችን ስለምንመዘው ቱባ ቱባ ገንዘብ እናስብ። የአንድ ምሽት የእራት ግብዣ ዋጋ ስድስት ቤተሰብ

ከሚያስተዳድር አባ ወራ የወር ደሞዝ ገዘፍ ያለ ሲሆን ምን ይባላል?። ዛሬ ዛሬ በአንዳንድ መሸታ ቤቶች ባንኮኒ ላይ ለአፍታ ደስታ የሚከፈለው የገንዘብ መጠን አብዛኛው ሠራተኛ እቁብ ካልገባ የማይቆጥረው ሲሆንና ገበሬው ደግሞ ያደለበውን ሰንጋ ካልሸጠ የማያየውን ሲያክልስ ምን እንላለን?። እጅግ እጅግ የባሱ ማወዳደርያዎችን መጥቀስ ይቻላል . . . እንግዲህ ለዚህ ነው ይበልጥ ወደ ራሳችን ማየትና ማገናዘብ ግድ የሚለን።

እስቲ የምናባክነውን ገንዘብና በአፀፋው ያገኘነውን ጥቅም እንመዝንና ጥቂትም ቢሆን ለሌሎች ምን ያህል እንደሚጠቅም እናስተውል። በላይኛው ታሪክ ሁለት የፒዛ ቁጣዎች ከፈፀሙት ተአምር እንነሳና አንድ በጎ ነገር ማድረግ እንደምንችል እርግጠኛ እንሁን። እናም በቀና መንፈስ ለእኛ እዚህ ግባ በማይባል መጠንና ምንም በማይጎዳን ወጪ ሰዎች ሲጠቀሙ ከማየት ሌላ ምን የሚያስደስት ነገር ይገኛል። ከውጭ ተዘርግተው የሚጠብቁን ብዙ ሺህ መዳፎች እንዳሉ ከተረዳንና አንዱን እንኳን ለመጨበጥ ከደፈርን ይህ ከበቂ በላይ ነው፤ ብርታቱን ስናዳብር ደግሞ የበለጠ እጹብ ድንቅ ለተባለ ተግባር እንተጋለን። ብቻ . . . ቀና እንሁን።

መነሻ ሃሳብ : moral Stories.com -
"Your Chance of a Greater Good"
ጥር 2009 ዓ.ም. ላንጋኖ



## ሞክር !

እሸቱ በአንድ የገጠር መንደር ውስጥ ከልጅነቱ በጀመረው የአናፂነት ሥራ ይተዳደር ነበር። በእድሜም በኑሮም እየጠነከረ ሲመጣ ትዳር ለመመስረት ወሰነ። ለጋብቻ ያሰባት ደግሞ ባሻገር የምትኖረዋን የገበሬውን ልጅ ጀሚላን ነበር። ከመልከ መልካሚ ኮረዳ ጋር የድብቅ ፍቅር ከጀመሩ ከራርመዋል፤ ቃል እንደገባችለትና እንደምትወደው ቢያውቅም ወላጆቿን በአግባቡ ማስፈቀድ ስላለበት እንደ ሃገሩ ባህል ሁነኛ ሽማግሌዎችን መርጦ አማላጅ ወደ ቤተሰቦቿ ላከ።

ሽማግግሌዎቹ ያመጡለት መልስ ግን እንቢታም እሽታም ሳይሆን ለየት ያለና ያልተለመደ ሆነ። ይኸውም : "ልጄን ማግባት የሚችለው" አሉ አባቷ "ከበረቱ በየተራ ከምለቃቸው ሶስት በሬዎች መሃከል የአንዱን ጭራ ይዞ ማቆም ከቻለ ብቻ ነው!" የሚል ነበር። በመልሱ ግራ የተጋቡት አማላጆችም በጉዳዩ ላይ ከተወያዩ በኋላ ውሳኔአቸውን ማስቀየር ስላልቻሉ የሙከራውን ቀን ቆርጠው ተመለሱ። አይደርስ የለም የቀጠሮው ቀኑ ደረሰ። በእለቱ ጠዋት - እሸቱ ወደ ልጅቷ አባት ግቢ አመራና ከበረቱ ፊት ለፊት በተዘጋጀለት ስፍራ በተጠንቀቅ ቆሞ ይጠባበቅ ጀመር።

በረቱ ተከፈተና የመጀመሪያው በሬ ተንደርድሮ ወጣ። እሸቱ ካለበት አልተንቀሳቀሰም፤ ደነገጠ። ትልልቅ ሹል ቀንዶቹን በማስቀደም ተወርውሮ የወጣውን በሬ ጭራውን ለመያዝ አልደፈረም፣ ይልቁኑ ከሚቀጥሉት አንዱ የተሻለ ሊሆን ይችላል በሚል ግምት ቀጣዩን ለመሞከር አስቦ ጥጉን ይዞ ቆመ።

በመቀጠል ለሁለተኛው በሬ በረቱ ተከፈተ . . . ። እንደዚህ አይነት እጅግ ትልቅና ግዙፍ በሬም ሆነ ሌላ እንስሳ በህይወቱ አይቶም ሆነ ስለመኖሩ ሰምቶ አያውቅም። በሰፋፊ አፍንጫዎቹ ከሰውነቱ የሚያስወግደው አየር አካባቢውን በፉጨት እያደባለቀና በፊት እግሮቹ ሾህናዎች መሬቱን ከፉኛ እየደቃ ብቅ አለ። ይህኛው በሬ ጭራውን ለመያዝ ቀርቶ ለመጠጋትም የማይሞከር ሆነበት፤ በድንጋጤ እንደደነዘዘ የመጨረሻውን ለመሞከር ወስኖ . . . ይጠባበቅ ጀመረ።

ለመጨረሻ ጊዜ በሩ ሲከፈት . . . ሶስተኛው በሬ በዝግታ ወጣ። እሸቱ - ከሲታ ሰውነቱን እየጎተተ የወጣውን በሬ ሲያይ ደስ አለው፤ ፊቱ በፈገግታ እንደበራ "ይህ ነው የኔ በሬ - ጭራውን ጨምድጄ ቀጥ አድርጌ ማስቆም አይሳነኝም" በማለት በውስጡ ቃል እየገባ ከኋላው ለመወርወር ቦታውን አመቻችቶ ጠበቀ . . . ጠበቀና ከትክክለኛው ቦታ በትክክለኛው ሰዓት ወደ በሬው ጀርባ ዘለለ ምን ያደርጋል፤ አሳዛኝ መጨረሻ . . . <u>በሬው ጭራው ቆራጣ ነው!።</u>

ይህ ነው እንግዲህ የመጀመሪያ እድልህን አታሳልፍ አልያም (ከመጠራጠር - መሞከር) የሚያሰኘው። ህይወት በበርካታ እድሎችና ገጠመኞች የተሞላች ናት። አንዳንዶቹ በቀላሉ የሚፈፀሙና ደጋግሞ ለመሞከር የተመቹ ሲሆኑ ጥቂቶቹ ግን በሳል ውሳኔና ፈጣን እርምጃ የሚሹ በመሆናቸው እንደ እነዚህ አይነቶቹ እድሎች በይሆናል ወይም ባልተጨበጠ ግምት የማይታለፉና አንዴ ካመለጡ፤ ዳግም ስለመገኘታቸው ምንም ስለማይታወቅ፤ ምንጊዜም በመጀመሪያው ዕጣ መሰንዘር፣ በቀደመው አጋጣሚ መሞከር ያለባቸው ናቸው። ስለዚህ "ከማይተማመኑበት አጋጣሚ የሚሳተፉበትን ድርጊት መምረጥ ብልህነት ነው" (የኔ)

ምንጭ፡ የሥነ ምግባር ትምህርቶች ድረ ገጽ
ደራሲ፡ ያልታወቀ - (የሕዝብ)
ሰኔ 18 2007 * አዲስ አበባ

# የሾርባው ታሪክ

አንድ ቀን የሙላህ ናስሩዲን የድሮ ጓደኛ ትልቅ ዶሮ ይዞ የጥንት ጓደኛውን ሊጠይቅ መጣ። የሙላህ ባለቤት ዶሮውን ጥሩ አድርጋ ሰራችና እንግዳውና ቤተሰቡ ምርጥ እራት ተመግበው አደሩ።

በነጋታው ጠዋት የሙላህ ሚስት ያዘጋጀችው የዶሮ ሾርባ እጅግ ጣፋጭ ነበር። የሙላህ ጓደኛ አስደሳቹን የአጭር ጊዜ ቆይታ አጠናቆ ወደ መጣበት ሊመለስ ተነሳ። ሙላህም በጥንት ጓደኛቸው ያልተጠበቀ ጉብኝትና አስደናቂ ስጦታ ልባቸው ስለተነካ የምስጋና ካርድ አዘጋጅተው፣ በላዩ ላይ ልባዊ ስሜታቸውን የሚገልጽ ቃል በማስፈር አበረከቱለት።

የሙላህ ጓደኛ ተሰናብቷቸው ከሄደ ከአንድ ሰዓት በኋላ የውጪው በር ተንኳኳ። በሩ እንደተከፈተ የመጣው ሰው ሰላምታ በማቅረብ . . . "ትልቅ ዶሮ ይዞ የመጣው የሙላህ ጓደኛ - ጓደኛ ነኝ" በማለት ራሱን አስተዋወቀ። ሙላህ ለጓደኛቸው ጓደኛ ተቃውሞም ሆነ አላስፈላጊ ቃል አላሰሙም። ወደ ውስጥ አስገብተው ትንሽ አርፎ ምሳ እንዲበላ ጠየቁት። የተዘጋጀው ምሳ ዶሮ ወጥ ነበር፤ እንግዳው ሁለት ጉንጮቹን እየሞላ ግጥም አድርጎ በላና ሲጠግብ፣ ስላቀረቡለት ጣፋጭ ምግብ አመስግኖ ወጣ።

ከሌላ ሦስት ሰዓት በኋላ የቤቱ በር እንደገና ተንኳኳ። ሙላህ በሩን ከፈቱ፤ ፊት ለፊታቸው የቆመውን ሰው ከዚህ በፊት አይተውት አያውቁም። ፈገግ ብሎ፤ "እኔ ዶሮ ይዞ የመጣው ጓደኛዎ - ጓደኛ - ጓደኛ ነኝ" አላቸው።

ትህትናና ተካፍሎ መብላትን ሲያስተምሩ የኖሩት ሙላህ፤ የጓደኛቸውን ጓደኛ - ጓደኛ አላገዱትም። ገብቶ እንዲቀመጥና እራት ሲሰናዳ እንዲመገብ ጋበዙት፣ ሰውየውም በጥድፊያ ገብቶ ተቀመጠ። እራቱ ሲደርስ የቀረበለትን የዶሮ ሾርባ ምጥጥ አርጎ በማጣጣም ተሰናብቷቸው ሄደ።

የገባው ሰው በልቶ ጠጥቶ ሲሄድ በተወሰነ የሰዓት ልዩነት ሌላው ያልታወቀ እንግዳ በሩን ያንኳኳል። በዶሮው ምክንያት የተፈጠረው "የጓደኛዎ - ጓደኛ - ጓደኛ" የሚለው ታሪክ ድግግሞሹ ቀጠለ። የሙላህ ሚስት ጓዳቸው ውስጥ አንዴ ወጡን፣ አንዴ ሾርባውን ሌላ ስጋ እየጨመሩ መቀቀል ስራቸው ሆነ። ዶሮው ተጠናቀቀና . . . የሙላህ ፍየልም ተጋመሰች። ሙላህ በሆዳቸው "የምን ጉድ ነው? አሁንስ ቤቴ ወደ ምግብ ቤትነት መቀየሩ ነው እንዴ?" እያሉ ቢያጉረመርሙም ሁኔታው ግን አልተቀየረም። በመጨረሻ የፍየሏ አጥንትና ቅንጥብጣቢ ጥንቅቅ ብሎ ያለቀ ምሽት ፍፃሜዋ ተረጋገጠ።

በቀጣዩ ቀን ጠዋት ላይ የተለመደውን ታሪክ ይዞ የመጣው ሰው አልተከለከለም፡፡ "እኔ ትልቅ ዶሮ ይዞ የመጣው ጓደኛዎ - ጓደኛ - ጓደኛ - ጓደኛ - ጓደኛ . . . ነኝ" አላቸው። አስገብተው ምግብ እንዲበላ ጋበዙት። ጣፋጩን የዶሮ ሾርባ እያሰበ ከንፈሩን ደጋግሞ በመላስ ሲጠባበቅ የነበረው እንግዳ፣ የጓጓለት የዶሮ ሾርባ ቀረበለት። ማንኪያውን አነሳና ተንሰፍስፎ አንዴ ሳብ አደረገው፤ ወዲያው "እንዴ! ይሄማ የዶሮ ሾርባ አይደለም፣ የሞቀ ውሃ ነው!" በማለት ጮኸ።

"አይመስለኝም" አሉት ሙላህ በጥቂቱ ፈገግ ብለው።

"ቅመሱት? እስቲ ቅመሱት? የሞቀ ውሃ ነው" አላቸው።

ሙላህም፡- "አይመስለኝም ልጄ! ይህ እኮ - የዶሮ ሾርባው - ሾርባ - ሾርባ - ሾርባ - ሾርባ . . . ነው" ብለው መለሱለት።

ሰውየው ምንም ሳይናገር አፉን በመዳፉ እያበሰ፣ ከቤቱ ወጥቶ ሄደ፡፡

ከታሪኩ የምንማረው አብይ መልክት፤ አንዳንድ ሰዎች ለጋስነታችሁን፣ እንግዳ ተቀባይነታችሁንና ቸርነታችሁን ተገን አድርገው ሊጠቀሙባችሁ ይሞክራሉ። በኃይል አትጋፈጧቸው አልያም አላስፈላጊ ቃል አትጠቀሙ፣ በምትኩ ወደ ውስጥ አስገቧቸውና ተገቢውን ትምህርት ስጧቸው።

ደግነት መልካም ነው፣ ጨዋነት፣ ትህትናና በጎ አድራጊነት የተመረጡ ባህሪያት ናቸው። እንደዚህ አይነት ሰዎች ክፉ፣ ንፉግና አስመሳይ መሆን አይችሉም፣ ልሁንም ቢሉ የአስተውሎትና የሚዛናዊ ህሊና ባለቤቶች ስለሆኑ አይሆንላቸውም። ነገር ግን ዛሬ ዛሬ በስፋት እንደምናስተውለው በብልጣ ብልጦች ይጠቃሉ። ደግ በማድረጋቸው ብቻ በሆዳሞችና በተንኮለኞች ክፉኛ ይበደላሉ . . .።

ወዳጆቼ፡- እስቲ በዚህ ረገድ የተጎዱ ወገኖቻችንን እናስብ። በቅርብም በሩቅም፣ በየትኛውም አካባቢ በደግነታቸውና በመልካም ሥራቸው ምክንያት ለውድቀት የተዳረጉ ሰዎችን ለመርዳትና ቀንበራቸውን ለመጋራት ባላቸው ጽኑ መንፈስ ብቻ፤ ወርቅ አበድረው አፈር የተመለሰላቸው ቅን ሰዎች እጅግ ብዙ ናቸው። አንዳንድ አልጠግብ ባዮች እኩይ ባህሪያቸውን በወዳጅነት ገጽ ሸፍነው፤ አርቀው የወጠኑትን ጥቅም ለማግኘት ብቻ ቀረቤታን ይፈጥራሉ። በመልካም ሰዎች ሩህሩህ ባህሪይና ቅን አስተሳሰብ ላይ ተረማምደው የቋመጡለትን ውጤት እስኪቀዳጁ ምንም የማይታወቅባቸው እነኝህ - "የበግ ለምድ የለበሱ ቀበሮዎች" ውሎ አድሮ ደጉ ሰው የሚከፍለው ዋጋና የሚደርስበት ስቃይ ምናቸውም አይደለም።

ከሃዲዎችን፣ አጭበርባሪዎችን፣ የራሳቸው ያልሆነን የሚመኙ ክፉዎችን በማግለል፣ በመጥፎ ምግባራቸው እንዲያፍሩና እንዲሸማቀቁ በማድረግ . . . የዋሆቹን ማበረታታትና ትሁቶቹን ማጽናናት እንችላለን። ከመሸጉበት ማህበራዊ ጫካ አውጥተን የሴራ

ጭምብላቸውን ገፈንና እርቃናቸውን አጋልጠን፣ ሌሎች ብዙ ብዙ መልካም ሰዎቻችንን ከመሰል ጥፋት ማዳን የምንችለውም በዚህ ብቻ ነው።

እናንተ ለቅን ህሊና የተገዛችሁ፣ ማስተዋል፣ ደግነትና እንግዳ ተቀባይነትን የተቸራችሁ ሁሉ፤ የመምህሩ ሙላህን "የሾርባ ታሪክ" አስታውሱ፣ የማታለያ ወጋቸውን አዳምጡና ማስመሰያ ስብከታቸውን ታዘቡና በዘዴ አስገብታችሁ የዕድሜ ልክ ትምህርት ስጧቸው። እንደ ሙላህ "የሾርባው - ሾርባ - ሾርባ - ሾርባ . . . "

*መቼም "ሆዳም ሰውና ባዶ ጠርሙስ አንድ ናቸው" ይባላል፡፡ ለምን? ብትሉ፤ "ሁለቱም ሆድና አንገት እንጂ ራስ የላቸውም"።* ቢሆንም ሳትታክቱ ንገሯቸው።

*ደግ - ደጎቹን ያበርክትልን !*

- *ሙላህ ፡ የእስልምና ሃይማኖት መምህር ማለት ነው*

ምንጭ ፡ ከ አንቶኒ ዲ ሜሎ "የወፎች ዝማሬ" ስብስብ ታሪኮች መጽሃፍ - "የሾርባው ታሪክ"
Anthony de Mello S. J. "THE SONG OF THE BIRD" Title:" THE SOUP STORY"

*መስከረም* - 2008 (ዓ.ም.) * አዲስ አበባ

============= ✱✱✱ ============